፫ አልቦ ፡ ዘቦአ ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ፡ ማኅደር ፡ ዘእን
በለ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ።

፬ ወዘእንበለ ፡ ዘዐቀበ ፡ ሥጋሁ ፡ በንጽሕ ፡ እም
ብእሲት ፡ በድንግልና ።

፭ ወትነብር ፡ ዕፁታ ።

፮ ወካህናተ ፡ ሰማይ ፡ የአጥንዋ ፡ ኵሎ ፡ ጊዜ ፡
ዘእንበለ ፡ ጽርዓት ።

## ምዕራፍ ፡ ፯

### በእንተ ፡ ስእለተ ፡ ሐዋርያት ።

፩ ወተስእልዎ ፡ ሐዋርያት ፡ ለእግዚእነ ፡ ወይ
ቤልዎ ፡ ናሁ ፡ እግዚእነ ፡ ንሕነ ፡ ኀደግነ ፡ ኵሎ ፡ ወተ
ለውናከ ፡ ምንት ፡ እስብነ ።

፪ ወአውሥአሙ ፡ እግዚእነ ፡ ለዐሠርቱ ፡ ወክ
ልኤቱ ሐዋርያት ፡ አማን ፡ እብለክሙ ፡ ባው ፡ ምስሌየ ፡
በግህደት ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ አቡየ ፡ ዘበሰማያት ።

፫ አመ ፡ ዳግም ፡ ምጽአቱ ፡ ለአቡየ ፡ ዲበ ፡ ፲ወ፪
መናብርት ፡ ትነብሩ ፡ በግህደት ፡ በብሩህ ፡ ገጽ ፡ ወትኴንኑ
፲ወ፪ተ ፡ ሕዝበ ፡ ፳ኤል ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡



፫ ከአብ ፡ ከወልድ ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በቀር ፡
አንድ ፡ ስንኳ ፡ በዚህ ፡ ቦታ ፡ የገባ ፡ የለም ፡ አለ ፡ በሦስቱ
ፈቃድ ፡ የሚገቡባት ፡ ስለሆነ ።

፬ ከሴት ፡ ርቆ ፡ በድንግልና ፡ በንጽሕና ፡ አመን
ዝራ ፡ ከመሆን ፡ ሰውነቱን ፡ ከጠበቀ ፡ ሰው ፡ በቀር ።

፭ ተዘርግታ ፡ ትኖራለች ፡ እንጂ ፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡
ያልገባባት ።

፮ ካህናተ ፡ ሰማይም ፡ ሁልጊዜ ፡ ሳያቋርጡ ፡
ያጥኗታል ።

## ፯ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### ስለ ፡ ሐዋርያት ፡ ጥያቄ ።

፩ ሐዋርያትም ፡ ጌታችንን ፡ ሁሉን ፡ ትተን ፡
እነሆ ፡ ተከተልንህ ፡ ዋጋችን ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ ጌታችን
ብለው ፡ ጠየቁት ።

፪ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ ዐሥራ ፡ ሁለቱ
ሐዋርያትን ፡ ሰማያዊ ፡ አባቴ ፡ በሥጋ ፡ በብርሃን ፡ ወዳ
ዘጋጀት ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ (ከኔ ፡ ጋር) ፡ መከልከል ፡
ሳይኖርባችሁ ፡ በውነት ፡ ግቡ ፡ እላችኋለሁ ፡ ብሎ ፡ መለ
ሰላቸው ።

፫ እግዚአብሔር ፡ በብሉይ ፡ በሐዲስ ፡ እንደተና
ገረ ፡ በምመሰገንበት ፡ ደብረ ፡ መቅደሴ ፡ በተሠራበት ፡
በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ እሑድና ፡ ቀዳሚትን ፡ ያከበሩ
ትን ፡ ሕጌን ፡ ያልሻሩትን ፡ በኔ ፡ ሥርዓት ፡ ጸንተው ፡ መከራ

በመጽሐፍ ፡ ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ የዓቅቡ ፡ ሰንበታትየ
ወኢያረኵሱ ፡ ሕግየ ፡ ወትዓገሡ ፡ በሥርዓትየ ፡ አበው
ያሙ ፡ ውስተ ፡ ደብረ ፡ መቅደስየ ፡ ወአስተፌሥሐሙ ፡
በቤተ ፡ ጸሎትየ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

## በእንተ ፡ ኅርየተ ፡ መሥዋዕት ።

፩ ወይከውኑ ፡ ኅሩየ ፡ መሥዋዕትየ ፡ ወቍርባንየ ።

፪ ቤትየሰ ፡ ቤተ ፡ ጸሎት ፡ ይሰመይ ፡ ይቤ ፡
እግዚአብሔር ፡ ለኵሉ ፡ አሕዛብ ።

፫ ሰንበት ፡ ብሂል ፡ ኢኮነት ፡ ዕለት ፡ አላ ፡ አነ ፡
ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ባቲ ፡ ተንሣኢየ ፡ አግ
ሀድኩ ፡ ለኵሉ ።

፬ ወውእቶሙሰ ፡ ሰብእ ፡ እለ ፡ ወፅኡ ፡ እምሲ
አል ፡ ዕሡራን ፡ ከሳውዲሆሙ ፡ በሰናስለ ፡ እሳት ፡



ሁሉ ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ ሰጥቼ ፡ ደስ ፡ አሰ
የተቀበሉትን ፡ መንግሥት ፡ ሰማያትን ፡ አወርሳችዋለሁ ፡
ኛቸዋለሁ ፡ እንዳለ ፡ የባሕርይ ፡ አባቴ ፡ አብ ፡ በኔ ፡ ሕልውና ፡ ሆኖ ፡
እንዳለ ፡ የባሕርይ ፡ ክብሩ ፡ ፪ኛ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ በዐሥራ ፡ ሁለት
በባሕርይ ፡ ክብሩ ፡ ፪ኛ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ በዐሥራ ፡ ሁለት
ወንበር ፡ ትቀመጣላችሁ ፡ በባለሟልነት ፡ ተገልጻችሁ ፡
ዐሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ነገደ ፡ እሥራኤልን ፡ ትገዛላችሁ ።
አሁን ፡ አብ ፡ ተገልጠ ፡ ይመጣል ፡ ማለት ፡ አይደለም ፡
የወልድን ፡ ለአብ ፡ ሰጥቶ ፡ መናገር ፡ ነው ፡ እንጂ ።

## ፮ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ መሥዋዕት ፡ መመረጥ ።

፩ ለኔ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሆናሉ ፡
የተሠዋው ፡ ሥጋየ ፡ ደምየም ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ይሆ
ናል ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳሉ ፡ በሚገባ ፡ ለተቀበሉት ፡ ምእ
መናን ፡ ጽምዓ ፡ ነፍስ ፡ ረሀበ ፡ ነፍስ ፡ ያርቅላቸዋል ።

፪ እግዚአብሔር እኔ ፡ አድሬበት ፡ የምኖርበት ፡
ቤት ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አስ
ተምሯል ።

፫ እግዚአብሔር ፡ በዕለተ ፡ ሰንበት ትንሣኤየን ፡
ለፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ገልጬባታለሁና ፡ ሰንበት ፡ ማለት ፡
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ በቁሙ ፡ ዕለት ፡ ማለት
አይደለችም ፡ አለ ።

፬ በእሳት ፡ ሰንሰለት ፡ አንገታቸውን ፡ ታስረው ፡
ከሲኦል ፡ የወጡ ፡ እሊህ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ አንድ ፡ አንዱ ፡

ከመ ፡ ዘአምስጡ ፡ ይረውጹ ፡ ለለ ፡ ፩፩ ፡ ምስለ ፡ ካልዑ
እለ ፡ ይጐይዩ ፡ ወይትባደሩ ፡ ወኢየአርፉ ፡ መዓልተ
ወሌሊተ ።

፭ ወይበጽሑ ፡ እስከ ፡ አጽናፈ ፡ ሰማይ ፤ ወእ
ስከ ፡ አጽናፈ ፡ ምድር ።

፮ ወይመስሎሙ ፡ ዘይገብኡ ፡ ኀቤሃ ፡ እምሥ
ራቅ ፡ ወእስከ ፡ ምዕራብ ፡ እምደቡብ ፡ ወእስከ ፡ ሰሜን ።

፯ ወይብሉ ፡ ንዒ ፡ አ ፡ እምነ ፡ ኵሎ ፡ ጊዜ ።

፰ ሶበሰ ፡ አእመርነ ፡ ዘከመዝ ፡ ኵንኔ ፡ እምኢ
ወሀብነ ፡ ርእሰነ ፡ ለንዋም ።

፱ አ ፡ ፍቁራንየ ፡ እለ ፡ ሀለውክሙ ፡ ውስተ ፡
ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ መኑ ፡ ይነግረክሙ ፡ ከመ ፡ ኢትምጽኡ ፡
ብሔረ ፡ ሕማም ።

፲ አምኀየስነ ፡ ሶበ ፡ ኢተፈጠርነ ፡ እምንትፌ
ጠር ።

፲፩ ወሶበ ፡ ኮነ ፡ ንቅወተ ፡ ዶርሆ ፡ ለጸቢሐ ፡
ሰኑይ ፡ ይስህቡ ፡ ውእተ ፡ ሰናስለ ፡ ዘእሳት ፡ መላእክተ ፡
ጽልመት ፡ ወያመጽእዎሙ ፡ ለውእቶሙ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡
ቅጽበተ ፡ ዓይን ።



እያንዳንዳቸው ፡ በመዓልትም ፡ በሌሊትም ፡ ሳያርፉ ፡ እየ
ተሽቀዳደሙ ፡ ከሚሸሹ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ እናመልጣለን ፡
እንደማለት ፡ ይገሠግሳሉ ።

፭ ከምድር ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ሸሽ
ተው ፡ የሚያመልጡ ፡ ይመስላቸዋል ።

፮ ወደሲኦል ፡ የሚመለሱ ፡ መስሏቸው ፡ ከሰሜን ፡
እስከ ፡ ደቡብ ፡ ከምዕራብ ፡ እስከ ፡ ምሥራቅ ፡ ድረስ ፡
ይደርሳሉ ።

፯ እናታችን ፡ ዕለተ ፡ ሰንበት ሆይ ፤ ዕለት ፡ ዕለት
ፈጥነሽ ፡ ሁልጊዜ ፡ ድረሽልን ፡ ይላሉ ።

፰ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጽኑዕ ፡ ፍዳ ፡ ወዳለበት ፡ ገሃ
ነመ ፡ እሳት ፡ መውረድ ፡ እንዳለስ ፡ ዐውቀን ፡ ቢሆን ፡
ኑሮ ፡ ሰውነታችንን ፡ ለአንድ ፡ ጊዜ ፡ ሽልብታ ፡ ስንኳን ፡
ባልሰጠንም ፡ ነበር ።

፱ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የምትኖሩ ፡ የምንወዳችሁ ፡
ወንድሞቻችን ፡ ሆይ ፡ ጽኑዕ ፡ መከራ ፡ ወዳለባት ፡ ቦታ ፡
እንዳትመጡ ፡ ማን ፡ በነገራችሁ ።

፲ ተፈጥረን ፡ ገሃነም ፡ ከምንወርድ ፡ ጥንቱን ፡ ባል
ተፈጠርን ፡ ይሻለን ፡ ነበር ፡ ይላሉ ።

፲፩ እሑድ ፡ ለሰኞ ፡ አጥቢያ ፡ ዶሮ ፡ በሚጮኽ
በት ፡ ጊዜ ፡ የጨለማ ፡ አበጋዞች ፡ አጋንንት ፡ ያን ፡ የእ
ሳት ፡ ሰንሰለት ፡ ባንገታቸው ፡ አስረው ፡ እየሳቡ ፡ እሊያን
ሰዎች ፡ እንዳይን ፡ ጥቅሻ ፡ ፈጥነው ፡ ያመጧቸዋል ።

፲፪ ወትትፌሣሕ ፡ ሲኦል ፡ ሶበ ፡ ትሰምዕ ፡ ድም
ጸሙ ፡ ለሰብእ ።

፲፫ ወያወርድዎሙ ፡ ለእሙንቱ ፡ ሰብእ ፡ ውስተ ፡
ሲኦል ።

፲፬ ወይበክዩ አንብዓ ፡ መሪረ ፡ እንዘ ፡ ይብሉ ፡
ወይ ፡ ለነ ፡ አሌ ፡ ለነ ፡ አይቴ ፡ ሀለወት ፡ ፍቅ
ርትነ ፡ ብእሲትነ ፡ ወውሉድነ ፡ ወአዕርክቲነ ፡ ወፍ
ቁራኒነ ፡ ወአግብርቲነ ፡ ወአዕማቲነ ፡ ዘኢይትወሐሱነ ፡
ወኢይስእሉ ፡ በእንቲአነ ።

፲፭ ወይትሐቀፉ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ ወይስሐቡ ፡
፩፩ ፡ ምስለ ፡ ካልኡ ፡ ወይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ሲኦል ።

፲፮ ወበህየ ፡ ዓቢየ ፡ ብካየ ፡ ይበክዩ ፡ እስከ ፡
ያድለቀልቅ ፡ እምቃሎሙ ፡ ሰማይ ፡ ወምድር ።

፲፯ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብዙኃ ፡
የኀዝኑ ፡ በእንቲአሆሙ ።

፲፰ ወመላእክተ ፡ ሰማይኒ ፡ ይከልዑ ፡ አክሊ
ላቲሆሙ ፡ እምዲበ ፡ ርእሶሙ ።

፲፱ ወጻድቃን ፡ ይበክዩ ፡ በውስተ ፡ ገነት ፡ አን
ብዓ ፡ መሪረ ፡ በእንቲአሆሙ ፡ እስመ ፡ መልአ ፡ አውያ
ቶሙ ፡ ወአንብዖሙ ፡ ይበጽሕ ፡ መጠነ ፡ ብረኪሆሙ ።



፲፪ ሲኦልም ፡ የሰዎችን ፡ ድምፅ ፡ በሰማች ፡ ጊዜ
ደስ ፡ ይላታል ።

፲፫ እሊያን ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ያወርድዋ
ቸዋል ።

፲፬ የምንወዳት ፡ ሚስታችን ፡ ልጆቻችን ፡ ባል
ንጀሮቻችን ፤ ወዳጆቻችን ፤ ወንዶችና ሴቶች ፡ አገል
ጋዮቻችን ፡ ስለኛ ፡ ይቅርታ ፡ የማይለምኑ ፡ የማይዋሱን ፡
ስለ ፡ ምንድነው ፡ ወዴትስ ፡ አሉ ፡ ወዮልን ፡ ወዮታ ፡ አለ
ብን ፡ እያሉ ፡ መሪር ፡ እንባን ፡ እንደክረምት ፡ ጐርፍ ፡
ያፈሳሉ ፡ ያለቅሳሉ ።

፲፭ አንዳንዱም ፡ ከአንዱ ፡ ጋር ፡ እርስ ፡ በርሳቸው
እየተሳሳቡ ፡ እየተቃቀፉ ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ይወርዳሉ ።

፲፮ ሰማይና ፡ ምድርም ፡ አሰምተው ፡ ከመጮኽ
ቸው ፡ የተነሣ ፡ እስከ ፡ መናወጽ ፡ ደርሰው ፡ በዚህ ፡ ፈጽ
መው ፡ ያለቅሳሉ ።

፲፯ አብና ፡ ወልድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በርሳቸው
ምክንያት ፡ ፈጽመው ፡ ያዝናሉ ።

፲፰ መላእክተ ፡ ሰማይም ፡ በተፈጥሮ ፡ ወንድሞ
ቻቸው ፡ ናቸውና ፡ በአጋንንት ፡ እጅ ፡ ተይዘው ፡ ጨለማ፡
ለብሰው ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ሲወርዱ ፡ ባይዋቸው ፡ ጊዜ ፡
የብርሃን ፡ አክሊላቸውን ፡ ከራሳቸው ፡ ያወርዳሉ ።

፲፱ ጻድቃንም ፡ ዕንባቸው ፡ ከጕልበታቸው ፡ ልክ ፡
እስኪደርስ ፡ ስለወንድሞቻቸው ፡ ስለኃጥአን ፡ በገነት ፡
ሁነው ፡ ምርር ፡ ብለው ፡ ያለቅሳሉ ፡ መሪር ፡ ዕንባን ፡ ያፈ
ሳሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፷ ።

### በእንተ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ።

፩ ወአንትሙ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ ኢትት
ሐከዩ ፡ ገይሠ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፡
ሠርከ ፡ ወነግሀ ።

፪ ወሶበ ፡ ተሐውሩ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ኢይምሰልክሙ ፡ ፅሩዓነ ።

፫ አንትሙሰኬ ፡ ትዌስኩ ፡ ወትረብሑ ፡ ክል
ኤተ ረባሐ ፡ ፩፡ ለነፍስክሙ ፡ ወ፩ ፡ ለተግባርክሙ ።

፬ ወእንዘ ፡ ሀሎክሙ ፡ ውስተ ፡ ተግባርክሙ ፡
ሶበ ፡ ትሰምዑ ፡ መጥቅዓ ፡ ሩጹ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
በከመ ፡ ይቤ ፡ ጳውሎስ ፡ እንሰ ፡ በድርየኒ ፡ ፈጸምኩ ፡
ወሃይማኖትየኒ ፡ አቀብኩ ፡ ወሠለጥኩ ፡ እንከሰኬ ፡ ጽኑሕ
ሊተ ፡ አክሊለ ፡ ጽድቅ ፡ ዘየዓስየኒ ፡ መኰንነ ፡ ጽድቅ ።

፭ ከማሁ ፡ ሩጹ ፡ ወብድሩ ፡ ክርስቶስሃ ፡ ትርከቡ ፡
ወመንግሥተ ፡ ዚአሁ ፡ ትረሱ ።



## ፷ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### ስለ ፡ ካህናትና ፡ ዲያቆናት ።

፩ እናንተ ፡ ካህናት ፡ ዲያቆናት ፡ በጧት ፡ በማታ ፡
በመዓልትም ፡ በሌሊትም ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
መገሥገሥን ፡ አታቋርጡ ፡ ቸል ፡ አትበሉ ።

፪ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሔዳችሁ ፡ ጊዜም ፡
ሥራ ፡ መፍታት ፡ አይምሰላችሁ ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡ ነን ፡
አትበሉ ።

፫ እናንተስ ፡ አንዱ ፡ ሥራችሁ ፡ የሚያከናውን ፤
አንዱ ፡ ለነፍሳችሁ ፡ ጥቅም ፡ የምታገኙበትን ፡ በሁለት ፡
ወገን ፡ ረብሕ ፡ ታገኛላችሁ ፡ በትሩፋት ፡ ላይ ፡ ትሩፋትን ፡
ትጨምራላችሁ ።

፬ ሥራ ፡ በመሥራት ፡ ላይ ፡ ሳላችሁ ፡ ደወል ፡
ሲመታ ፡ የደወል ፡ ድምፅ ፡ በሰማችሁ ፡ ጊዜ ፡ ቅዱስ ፡
ጳውሎስ ፡ እኔስ ፡ ከቢጽ ፡ ሐሳዊ ፡ ጋር ፡ በማስተማር ፡
እሽቅድድሜን ፡ ፈጸምሁ ፡ ሃይማኖቴንም ፡ ጠበቅሁ ፡
እንግዲህስ ፡ ወዲህ ፡ ዋጋዬን ፡ የሚሰጠኝ ፡ ፈታሒ ፡ በጽ
ድቅ ፡ ኰናኒ ፡ በርትዕ ፡ ጌታ ፡ የሕይወት ፡ አክሊል ፡ ያቆየ
ኛል ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረው ፡ እናንተም ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ ገሥግሡ ፡ ተሽቀዳደሙ ።

፭ እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ እናንተም ፡ የክርስቶስ
ማደሪያ ፡ ሁናችሁ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ ትወርሱ ፡
ዘንድ ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ለመሥራት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ ገሥግሡ ፡ ተሽቀዳደሙ ።

፮ ትግሁ ፡ ወጸልዩ ፡ ከመ ፡ ኢትባኡ ፡ ውስተ ፡ መንሱት ፡ እስመ ፡ መንፈስ ፡ ይፈቅድ ፡ ወሥጋ ፡ ይደክም ፡፡

፯ እስመ ፡ ኢተአምሩ ፡ ጊዜ ፡ ይመጽእ ፡ ሐዳስ ፡ በዓለ ፡ ቤት ፡ እመሂ ፡ ሠርከ ፡ ወእመሂ ፡ መንፈቀ ፡ ሌሊት ፡ ወእመሂ ፡ ጊዜ ፡ ይነቁ ፡ ዶርሆ ፡ ወእመሂ ፡ ጸቢሐ ፡፡

፰ ኢይርከብክሙ ፡ እንዘ ፡ ትነውሙ ፡፡

፱ ናሁ ፡ እብለክሙ ፡ ትግሁ ፡ ወጸልዩ ፡ ከመ ፡ ኢትባኡ ፡ ውስተ ፡ መንሱት ፡፡

፲ አስተፋጥኑ ፡ ገቢረ ፡ ሠናይ ፡ ትዕድዉ ፡ እሞት ፡ ውስተ ፡ ሕይወት ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፱ ፡፡

## በእንተ ፡ ኅርየተ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡፡

፩ ወአንትሙኒ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ ኅረይኩክሙ ፡ ወሤምኩክሙ ፡ በውስተ ፡ ከርሠ ፡ እምክሙ ፡ ረሰይኩክሙ ፡ ካህናት ፡ ፯ ፡ ወአስተማሰልኩክሙ ፡ በ፳፬ ፡ ወ፳፬ ፤ ካህናተ ፡ ሰማይ ፡ እለ ፡ የአጥኑ ፡ መንበርየ ፡፡



፮ ነፍስ ፡ ሥራ ፡ ልትሠራ ፡ ትወዳለች ፡ ሥጋ ፡ ግን ፡ ደካማ ፡ ነውና ፡ ወደመከራ ፡ ቅንፍ ፡ (ወደገሃነም) እንዳትገቡ ፡ ተግታችሁ ፡ ጸልዩ ፡፡

፯ ሲነጋም ፡ እንደሆነ ፡ ዶሮ ፡ ሲጮኽም ፡ እንደ ሆነ ፡ በመንፈቀ ፡ ሌሊትም ፡ በማታም ፡ እንደሆነ ፡ በተ ሐድሶ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ሃያ ፡ ሁለቱን ፡ ስነፍጥረት ፡ ፈጥሮ ፡ የሚገዛ ፡ ጌታ ፡ የሚመጣበትን ፡ ዕለትና ፡ ሰዓት ፡ አታውቁምና ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ በመሥራት ፡ ተግታችሁ ፡ ኑሩ ፡፡

፰ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ሳትሠሩ ፡ ሥራ ፡ ፈታችሁ ፡ እንዳያገኛችሁ ፡፡

፱ ወደ ፡ መከራ ፡ (ወደገሃነም) ፡ እንዳትገቡ ፡ እነሆ ፡ ተግታችሁ ፡ ጸልዩ ፡ እላችኋለሁ ፡፡

፲ ከሞት ፡ ነፍስ ፡ ድናችሁ ፡ ሕይወተ ፡ ነፍስን ፡ ታገኙ ፡ ዘንድ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፤ ተሽቀዳደሙ ፡፡

## ፱ኛ ፡ ምዕራፍ ፡፡

## ስለ ፡ ካህናትና ፡ ዲያቆናት ፡ መመረጥ ፡፡

፩ እናንተ ፡ ካህናትና ፡ ዲያቆናት ፡ ከናታችሁ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ መንበሬን ፡ በሚያጥኑ ፡ በሐያ ፡ አራቱ ፡ ካህናተ ፡ ሰማይ ፡ አስመስዬ ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ መርጬ ፡ ክህነትን ፡ ሰጥቼ ፡ ሾምኋችሁ ፡፡

፳ ወለክሙ ፡ ረሰይኩክሙ ፡ ትዕጥንዋ ፡ ለቅድ
ስት ፡ ታቦት ዘቀደስክዋ ፡ በደምየ ፡ ወአተብክዋ ፡ በዕፀ ፡
መስቀልየ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

### በእንተ ፡ ኃዲገ ፡ አበሳ ።

፩ ወአንትሙኒ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ ኢትትመ
ሰሉ ፡ ሕዝበ ፡ እስራኤል ፡ እስመ ፡ ግዙፋን ፡ ልብ ፡
እሙንቱ ።

፪ ወአንትሙሰ ፡ ኅድጉ ፡ አበሳ ፡ ለዘአበሰ ፡
ለክሙ ።

፫ ወኢታንብሩ ፡ ቂመ ፡ ውስተ ፡ ልብክሙ ፡
ትዕቢተ ፡ ወትዝኅርት ።

፬ ወአርኅቁ ፡ ሐሜተ ፡ እምኔክሙ ፡ እስመ ፡
ዝንቱሰ ፡ ግብር ፡ ኢኮነ ፡ ዘዚአየ ፡ አላ ፡ ዘሰይጣን ፡
ውእቱ ።



፳ እናንተንስ ፡ በተሰቀልኩበት ፡ መስቀል ፡ የባረ
ክኋት ፡ ከጐኔ ፡ በፈሰሰ ፡ ደሜ ፡ ያከበርኋት ፡ ንዕድ ፡ ክብ
ርት ፡ ታቦትን ፡ ታጥኑ ፡ ዘንድ ፡ እንድታጥኑ ፡ አድርጌያ
ችሁ ፡ ነበረ ፡ አለ ። በሚገባ ፡ ቢያገለግሉ ፡ ዋጋቸው ፡
መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ መስጠቱን ፡ በማይገባ ፡ ቢያገለግ
ሉት ፡ ግን ፡ ፍዳ ፡ ወደሚቀበሉበት ፡ ገሃነም ፡ ማውረ
ዱን ፡ መናገር ፡ ነው ።

## ፲ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### በደልን ፡ ይቅር ፡ ስለማለት ።

፩ እናንት ፡ ካህናት ፡ ዲያቆናት ፡ ሆይ ፡ ልቡና
ቸው ፡ የደነቆረ ፡ ነውና ፡ የእስራኤልን ፡ ወገኖች ፡ በግ
ብረ ፡ ገብ ፡ አትምሰሏቸው ፡ አብነት ፡ አታድርጓቸው ፡
የነሱን ፡ ግብር ፡ የያዛችሁ ፡ እንደሆን ፡ በነሱ ፡ ፍዳ ፡ ትያዛ
ላችሁ ።

፪ እናንተስ ፡ የበደላችሁን ፡ የወንድማችሁን ፡
ኃጢአት ፡ ይቅር ፡ በሉ ።

፫ ቂም ፡ በቀል ፡ ትዕቢትን ፡ ትዝኅርትን ፡ በልቡ
ናችሁ ፡ አታኑሩ ፡ ትዕቢት ፡ ለልቡና ፡ ትዝኅርት ፡ ያካ
ሔድ ፡ ያነጋገር ፡ ነው ፤

፬ ይህ ፡ ሐሜት ፡ ከሰይጣን ፡ የተገኘ ፡ ነው ፡ እንጂ
ከኔ ፡ የተገኘ ፡ አይደለምና ፡ ስውን ፡ ማማትን ፡ ከእናንተ ፡
አርቁ ።

፳፭ እስመ ፡ በትዕቢት ፡ ወበትዝኅርት ፡ ወድቀ ፡
ዲያብሎስ ፡ እመንበሩ ፡ ወተንሥተ ፡ ክብሩ ።

፳፮ ወእመሰ ፡ ተጻላእክሙ ፡ ምስለ ፡ ቢጽክሙ ፡
ፍጡነ ፡ ተዓረቁ ።

፳፯ ወኢተሀብዎ ፡ ፍኖተ ፡ ለሰይጣን ።

፳፰ ወዘእንበለ ፡ ይዕርብ ፡ ፀሐይ ፡ አቀርሩ ፡ መዓ
ተክሙ ፡ ከመ ፡ ኢይትመካህ ፡ ዲያብሎስ ፡ ወኢይበል ፡
ጸናዕኩ ፡ እምሥሉስ ፡ ቅዱስ ፡ ወሞዕክዎሙ ፡
ለቅዱሳን ።

፳፱ ወመሠጥኩ ፡ ፩ደ ፡ በግዓ ፡ እመርዔት ።

፴ ወሶበ ፡ ትበውዑ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ግድፉ ፡ እምላዕሌክሙ ፡ ኵሎ ፡ እከየ ፡ ምግባሪክሙ ።



፳፭ ዲያብሎስ ፡ በመታበይ ፡ በትዝኅርት ፡ ከተቀ
መጠበት ፡ ወንበር ፡ ወድቋል ፡ ከመዓርጉ ፡ ተዋርዷል ፡
ከክብሩ ፡ ተለይቷልና ፡ እናንተም ፡ ከመዓርጋችሁ ፡ እንዳ
ትዋረዱ ፡ ከክብራችሁ ፡ እንዳትለዩ ፡ ከዲያብሎስ ፡ ግብር
ሁሉ ፡ ተጠበቁ ።

፳፮ ሲሆን ፡ መጣላት ፡ አይገባም ፡ ነበር፡ ባይሆንም፡
ከአራቱ፡ ባሕርያት ፡ የተፈጠረ ፡ ሰውነታችሁ፡ ጽድቅም፡
ኃጢአትም ፡ ይስማማዋልና ፡ ሰይጣን ፡ አነሣሥቷችሁ ፡
ከወንድማችሁ ፡ ጋር ፡ ብትጣሉም ፡ ፈጥናችሁ ፡ ታረቁ ።

፳፯ ለሰይጣን ፡ የተሰናዳ ፡ መንገድ ፡ አትሁኑ ፡
አለ ፤ ሰይጣን ፡ እናንተን ፡ ምክንያት ፡ አድርጎ ፡ የሚያስ
ትበትን ፡ ሥራ ፡ አትሥሩ ።

፳፰ ዲያብሎስ ፡ ጽኑዓን ፡ ክቡራን ፡ ከሚሆኑ ፡ ኃይል
ጽንዕ ፡ የባሕርያቸው ፡ ከሚሆን ፡ ከሥላሴ ፡ ይልቅ ፡ በክ
ብር ፡ በሥልጣን ፡ እበልጣለሁ ፡ የሥላሴ ፡ ባለሟሎች ፡
ምእመናን ፡ በግብር ፡ ድል ፡ ነሣኋቸው ፡ ብሎ ፡
እንዳይመካ ፡ ፀሐይ ፡ ሳይገባ ፡ ፀሐይ ፡ ዕድሜያችሁ፡ ሳለ፡
ሳትታረቁ ፡ አትደሩ ።

፳፱ ከበጎች ፡ መንጋም ፡ አንዱን ፡ በግ ፡ ነጠቅሁ ፡
እንዳይል ፡ አለ ፤ ከምእመናንም ፡ አንዱን ፡ ምእመን ፡
ድል ፡ ነሣሁ ፡ ብሎ ፡ እንዳይመካ ፡ ታረቁ ።

፴ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ በምትገቡበት ፡
ጊዜ ፡ የሥራችሁን ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ ፈጽማችሁ ፡ ከእናንተ
አርቁ ፡ አለ ፤ ቂም ፡ በቀል ፡ ይዛችሁ ፡ አትግቡ ።

፲፩ ወዘትጸልዑ ፡ ለርእስክሙ ፡ ኢትግበሩ ፡ ዲበ ፡ ቢጽክሙ ።

፲፪ ወእመሰ ፡ አሠነይክሙ ፡ ለቢጽክሙ ፡ ሠናየ ፡ አነኒ ፡ አዓሥየክሙ ፡ እሤተ ፡ ሠናየ ።

፲፫ ወእመሰ ፡ ገበርክሙ ፡ እኪተ ፡ እከው ፡ ላዕሌክሙ ፡ መቅድሐ ፡ እሳት ፡ ዘአልቦ ፡ ዕረፍት ፡ ዘኢይጠፍዕ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

### በእንተ ፡ አውሥአ ፡ አቡነ ፡ ዘበሰማያት ።

፩ ለምንት ፡ ትብሉኒ ፡ አቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ኅድግ ፡ ለነ ፡ አበሳነ ፡ ወጌጋየነ ፡ ከመ ፡ ንሕነኒ ፡ ንኅድግ ፡ ለዘአበሰ ፡ ለነ ።

፪ ኢታብእነ ፡ እግዚኦ ፡ ውስተ ፡ መንሱት ።

፫ እስመ ፡ ይቤ ፡ በወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ እምቃልከ ፡ ትጸድቅ ፡ ወእምቃልከ ፡ ትትኰነን ።



፲፩ ሰው ፡ ሊያደርግላችሁ ፡ የማትወዱትን ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ እናንተም ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ አትሥሩ ።

፲፪ እናንተ ፡ ለወንድሞቻችሁ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ሥራ ብትሠሩ ፡ እኔም፡ በእናንተ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ሥራ ሠርቼ ፡ ደስ ፡ አሰኛችኋለሁ ።

፲፫ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ብትሠሩ ፡ ግን ፡ እኔም ፡ በናንተ ፡ ላይ፡ እስከ፡ ዘለዓለም ፡ ድረስ ፡ የማይጠፉ ፡ ሲጐርፍ ፡ የሚኖር ፡ ፍላቱ ፡ የማያቋርጥ፡ የእሳት፡ ጎርፍ ፡ አፈስባችኋለሁ።

## ፲፩ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### በሰማይ ፡ የምትኖር ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ ስለማለት።

፩ እኔ ፡ ያዘዝኳችሁን ፡ ትእዛዝ ፡ ባትፈጽሙ ፡ የሰማይ ፡ አባታችሁ ፡ እኛ ፡ የበደለንን ፡ የወንድማችንን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር ፡ እንል ፡ ዘንድ ፡ የኛን ፡ ፍጹም ፡ ኃጢአታችንን ፡ ይቅር ፡ በለን ፡ ለምን ፡ ትሉኛላችሁ ።

፪ አቤቱ ፡ ወደመከራ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ አታግባን ፡ ለምን ፡ ትሉኛላችሁ ። እንዲህ ፡ ማለት ፡ ከኃጢአት ፡ ነጽቶ ፡ በቅቶ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በኃጢአት ፡ ተለስኖ ፡ ነው ? ይላል ፡ እውነተኛው ፡ ንጉሥ ፡ ክርስቶስ ።

፫ በከበረ ፡ በገነነ ፡ ወንጌል ፡ ከአነጋገርህ ፡ የተነሣ ፡ ይፈረድብሃል ፡ ከአነጋገርህም ፡ የትነሣ ፡ ይፈረድልሃል ፤ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

## በእንተ ፡ ውሂበ ፡ ምጽዋት ።

፩ ለምንት ፡ ዘኢትሁብ ፡ እሁብ ፡ ትብል ።

፪ ወበከመ ፡ ሐሰውከ ፡ አንተሂ ፡ ለቢጽከ ፡ ወአ
ነኒ ፡ ምክዕቢተ ፡ እሔስወከ ።

፫ ይኄይስ ፡ ሠራቂ ፡ እምሐሳዊ ።

፬ ኢሰማዕከኑ ፡ ዘይቤ ፡ ጥበበ ፡ ሲራክ ፡ ዘባዕል ፡
ሐሳዊ ፡ ወዘነዳይ ፡ ዕቡይ ፡ ወዘአረጋዊ ፡ ዘማዊ ፡ እምኵሉ ፡
አስቆረረት ፡ ነፍስየ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ።

፭ ለምንት ፡ ኢተኃድጉ ፡ አበሳ ፡ ለቢጽክሙ ።

፮ ወለምንትኑ ፡ ትብሉኒ ፡ ኅድግ ፡ ለነ ፡ አበሳነ ፡
ወጌጋየነ ።



## ፲፪ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ ምጽዋት ፡ መስጠት ።

፩ ሳትሰጥ ፡ እሰጣለሁ ፡ እያልህ ፡ ሐሰት ፡ ለምን ፡
ትናገራለህ ፡ ከምን ፡ ኢገኘኸው ።

፪ አንተ ፡ ሳትሰጥ ፡ እሰጣለሁ ፡ ብለህ ፡ በወንድ
ምህ ፡ ሐሰት ፡ እንደተናገርህ ፡ እኔም ፡ እንኪያስ ፡ በማክ
በር ፡ ነዓ ፡ ኀቤየ ፡ ማለትን ፡ ትቼ ፡ ፍጹም ፡ ፍዳን ፡ ለመ
ቀበል ፡ ሑር ፡ እምኔየ ፡ ብዬ ፡ ገሃነም ፡ አወርድሃለሁ ።
ይህ ፡ ይሻላልን ፧

፫ ሐሰት ፡ ከሚናገር ፡ ሰው ፡ ሠርቆ ፡ ቀምቶ ፡
የሚመገብ ፡ ይሻላል ፡ ይድናል ፡ ማለት ፡ አይደለም ፡
ፍዳ ፡ ይቀልለታል ፡ ሲል ፡ ነው ፡ እንጂ ።

፬ ሲራክ ፡ ጥበብ ፡ በሚባል ፡ መጽሐፉ ፡ ከሁሉ ፡
ይልቅ ፡ የሚሰስን ፡ ሽማግሌን ፡ የሚታበይ ፡ ደሀን ፡ ሐሰት
የሚናገር ፡ ባለጠጋን ፡ ሰውነቴ ፡ ተጸየፈች ፡ አለ ። እግዚ
አብሔር ያለውን ፡ አልሰማኸምን ፡ አሁን ፡ እንዲህ ፡
ማለቱ ፡ የቀረውን ፡ ወዶና ፡ አመስግኖ ፡ የሚገባ ፡
ሆኖ ፡ አይደለም ፡ በሚበልጠው ፡ ሲገልጽና ፡ ሲመክር
ነው ፡ እንጂ ።

፭ ወንድሞቻችሁ ፡ ቢበድሏችሁ ፡ ስለምን ፡ ይቅር
ለእግዚአብሔር አትሉም ።

፮ እናንተ ፡ የወንድሞቻችሁን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር
ሳትሉ ፡ እኔን ፡ የኛን ፡ ፍጹም ፡ ኃጢአታችንን ፡ ይቅር ፡
በለን ፡ እያላችሁ ፡ ለምን ፡ ትለምኑኛላችሁ ።

፯ ወአነሂ ፡ ኢየኃድግ ፡ ለክሙ ፡ አበሳክሙ ።

፰ ወለምንት ፡ ትብሉኒ ፡ አቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡
ዘኢትገብሩ ፡ ዘእቤለክሙ ።

፱ አኮ ፡ ኪያየ ፡ ዘትጸውዑ ፡ አላ ፡ ለአቡክሙ ፡
ሰይጣን ፡ ትጼውዕዎ ።

፲ ወእመሰ ፡ ኮንክሙ ፡ ውሉድየ ፡ ኩኑ ፡ የዋሃነ ፡
ከመ ፡ ርግብ ፡ ወጠቢባነ ፡ ከመ ፡ አርዌ ፡ ምድር ።

፲፩ አነሂ ፡ እስመ ፡ የዋህ ፡ ወትሑት ፡ ልብየ ፡
እስመ ፡ አርዑትየኒ ፡ ሠናይ ፡ ወፆርየኒ ፡ ቀሊል ፡ ውእቱ ።



፯ እናንተ ፡ የወንድሞቻችሁን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር፡
ካላላችሁ ፡ እንኪያስ ፡ እኔም ፡ የናንተን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር
አልላችሁም ።

፰ ያዘዝኋችሁን ፡ ትእዛዝ ፡ ሳትፈጽሙ ፡ የሰማይ ፡
አባታችን፡ለምን ፡ ትሉኛላችሁ ፡ ያባቱን ፡ ትእዛዝ ፡ የፈ
ጸመ ፡ ልጅ ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፡ ማንኛቸውም ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡
ሁሉ ፡ ልጅ ፡ ይባላልን ? እስኪ ፡ አስተውሉት ።

፱ የሰማይ ፡ አባታችን ፡ እያላችሁ ፡ የምትጠሩት ፡
የግብር ፡ አባታችሁ ፡ ባላጋራችሁን ፡ ዲያብሎስን ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ እኔን ፡ አይደለም ።

፲ በውነት ፡ ልጆቼስ ፡ ከሆናችሁ ፡ እንደ ፡ እባብ ፡
ብልህ ፡ እንደ ፡ ርግብም ፡ የዋህ ፡ ሁኑ ፡ አለ ።
የእባብ ፡ ብልህነት ፡ እንዴት ፡ ነው ፡ ቢሉ ፡ ከመንገድ ፡
ዳር ፡ ሲተኛ ፡ ራሱን ፡ ቀብሮ ፡ ይተኛል ፡ እናንተም ፡ እራ
ሳችሁ ፡ እኔን ፡ አትክዱ ፡ ሲል ፡ አንድም ፡ ውሃ ፡ ሲጠጣ ፡
መርዙን ፡ ከየብስ ፡ አኑሮ ፡ ነው ፡ መርዙ ፡ ከውሃ ፡ የገባ ፡
እንደሆነ ፡ ተሰራጭቶ ፡ ያጠፋኛል ፡ ብሎ፡ እናንተም፡
ቂም ፡ በቀል ፡ ይዛችሁ ፡ አትጸልዩ ፡ ሲል ፡ ቂም ፡ በቀል ፡
ይዞ ፡ የጸለዩት ፡ ጸሎት ፡ አይረባም ፡ አይጠቅምምና ፡
እስመ ፡ ዘያነብር ፡ ቂመ ፡ ውስተ ፡ ልቡ ፡ ውክፍት ፡
ጸሎቱ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ።

ጸሎቱ ፡ ለመስተቀይም ፡ ከመ ፡ ዘርእ ፡ ዘወድቀ ፡
ማዕከለ ፡ አሥዋክ ፡ እንዲል ። ርግብም ፡ የዋህ ፡ ናት ፡ በቀል
የላትም ፡ እናንተም ፡ ኃዳግያን ፡ በቀል ፡ ሁኑ ፡ ሲል ፡ ነው ።

፲፩ ሸክሜ ፡ የቀለለ ፡ ቀንበሩ ፡ የለዘበ ፡ እኔም ፡
እንጂ ፡ ልቡናየ ፡ ትሑት ፡ ኀዳጌ ፡ በቀል ፡ ነኝ ።

፲፪ ወትረክቡ ፡ ዕረፍተ ፡ ለነፍስክሙ ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ፡፡

## በእንተ ፡ ገይሠ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡፡

፩ ወሶበ ፡ ተሐውሩ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ቁሙ ፡ ኀበ ፡ ኆኅቲሃ ፡ ወሰአሉ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር
ወበሉ ፡ አ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወልደ
እግዚአብሔር ሕያው ፡ ሥረይ ፡ ለነ ፡ አበሳነ ፡ ወጌጋ
የነ ፡ እመሂ ፡ በአእምሮ ፡ አው ፡ በኢያእምሮ ፡ ዘገበርነ ፡
ወንሕነኒ ፡ ኃደግነ ፡ አበሳ ፡ ለዘአበሰ ፡ ለነ ፡ በእንተ ፡
ስመ ፡ ዚአከ ፡፡

፪ ወውእተ ፡ ጊዜ ፡ ባው ፡ በንጹሕ ፡ ልብ ፡ ወይ
ሰምዐክሙ ፡ ጸሎተክሙ ፡ ከመ ፡ ዕጣን ፡ ንጹሕ ፡፡

፫ ወትበጽሕ ፡ ፍጡነ ፡ ስእለትክሙ ፡ ቅድሜሁ ፡
ለሰማያዊ ፡ ንጉሥ ፡ ከመ ፡ ቅጽበተ ፡ ዓይን ፡፡



፲፪ የእኔን ፡ ትእዛዝ ፡ የፈጸማችሁ ፡ እንደሆን ፡
በነፍሳችሁ ፡ ዕረፍትን ፡ ታገኛላችሁ ፡፡

## ፲፫ኛ ፡ ምዕራፍ ፡፡

## ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መሄድ ፡ ስለ ፡ ማዘውተር ፡፡

፩ እናንተ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ምእመናን
ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ለመሥራት ፡ ሥጋውን ፡ ደሙን ፡
ለመቀበል ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በምትሄዱበት ፡
ጊዜ ፡ የሕያው ፡ ባሕርይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አብ የባሕ
ርይ ፡ ልጁ ፡ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡
ስምህ ፡ ሕይወት ፡ መድኃኒት ፡ እንደሆነ ፡ አምነን ፡ ወንድ
ሞቻችን ፡ የበደሉንን ፡ በደል ፡ ይቅር ፡ አልን ፡ አንተም ፡
ፈጣሪያችን ፡ አውቀንም ፡ ሳናውቅም ፡ ቢሆን ፡ የበደል
ነውን ፡ ፍጹም ፡ በደላችንን ፡ ይቅር ፡ በለን ፡ እያላችሁ ፡
በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በር ፡ ቁማችሁ ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ አመልክቱ ፡፡

፪ ከቂም ፡ ከበቀል ፡ ንጹሕ ፡ ሁናችሁ ፡ ወደ ፡ ቤተ
ክርስቲያን ፡ በገባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ አማረ ፡
እንደ ፡ ተወደደ ፡ ዕጣን ፡ መዓዛ ፡ ልመናችሁን ፡ ደስ ፡
ብሎት ፡ ይቀበለዋል ፡፡

፫ በሰማያዊ ፡ ንጉሥ በክርስቶስ ፡ ዘንድ ፡ ልመ
ናችሁ ፡ እንደ ፡ ዓይን ፡ ጥቅሻ ፡ ፈጥና ፡ ትደርስላችኋለች ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

## በእንተ ፡ ተውኔት ።

፩ አ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ ኢትሑሩ ፡ ውስተ ፡
ተውኔት ፡ ወዘፈን ።

፪ ወአንስተ ፡ ካህናትኒ ፡ ኢይሑራ ፡ ውስተ ፡
ተውኔት ፡ እስመ ፡ ኅቤሆን ፡ ሀሎ ፡ ክህነት ።

፫ ወኢይሑራ ፡ ውስተ ፡ አምልኮ ፡ ጣዖት ፡ ወኢ
ይሕትታ ።

፬ ወለእመ ፡ ዘንተ ፡ ገብራ ፡ ዘእንበለ ፡ ይሰምዓ ፡
ቃለ ፡ አምታቲሆን ፡ እሥራ ፡ ዕለት ፡ ይጹማ ፡ እስከ ፡
የዓርብ ፀሐይ ፡ ከመ ፡ ዐቢይ ፡ ጾም ።

፭ ወብእሲሃ ፡ ሰሚዖ ፡ ዘንተ ፡ ለእመ ፡ ሰከበ ፡
ምስሌሃ ፡ ኢይባእ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ፪ሆሙ ፡
እስመ ፡ ኀደግዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።

፮ ውእቱሂ ፡ ይጹም ፡ ፵ ፡ ዕለተ ።
፯ ይጹሙ ፡ ወኢይባኡ ፡ ውስተ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን።

፰ ወበአፍአ ፡ ይስአልዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
እስከ ፡ ይፌጽሙ ፡ ንስሐሆሙ ።

፱ ርጉማን ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ያሰግሉ ፡ ወያጣ
ዕዉ ፡ ወይሰግዱ ፡ ለፀሐይ ፡ ወለወርኀ ፡ ወያመልኩ ፡



## ፲፭ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ ዘፈንና ፡ ጫዋታ ።

፩ እናንተ፡ ካህናትና፡ ዲያቆናት ፡ ሆይ ፡ ወደዘፈን ፡
ጫወታ ፡ ወደ ፡ ዋዛ ፡ ፈዛዛ ፡ ቤትም ፡ አትሂዱ ።

፪ የካህናት ፡ ሚስቶችም ፡ ክህነት ፡ በርሳቸው ፡
ዘንድ ፡ አለና ፡ ወደ ፡ ዘፈን ፡ አይሂዱ ።

፫ ጣዖት ፡ ወደሚመለክበት ፡ ቦታ ፡ የጣዖትን ፡
ግብር ፡ ለመመርመር ፡ አይሂዱ ፡ በነፍስ ፡ በሥጋ ፡ እንዳ
ይፈረድባቸው ፡ ማለት ፡ ነው ።

፬ ባሎቻቸው ፡ ቢመክሯቸው ፡ ቢያስተምሯቸው ፡
አንቀበልም ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ዘፈን ፡ ቢሄዱ ፡ ግን ፡ ፀሐይ ፡
እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ኩዳዴ ፡ ጾም ፡ ንስሐቸውን ፡
ሃያ ፡ ቀን ፡ ይጹሙ ።

፭ ባሏም ፡ ወደ ፡ ጠንቋይ ፡ ወደ፡ ዘፈን፡ መሄዱን ፡
ሰምቶ ፡ ከርሷ ፡ ጋር፡ ቢተኛ፡ እግዚአብሔርን በአምልኮ።
ትተውታልና፡ ሁለቱም፡ ወደ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ አይግቡ ።

፮ እርሱም ፡ ፵ ፡ ቀን ፡ ይጹም ።
፯ ጾማቸውን ፡ እስኪጨርሱ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ አይግቡ ።

፰ ንስሓቸውን ፡ እስኪፈጽሙ ፡ ድረስ ፡ ከቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ በውጭ ፡ ሁነው ፡ እግዚአብሔርን ፡
ይለምኑት ።

፱ እነሱን ፡ ማዳን ፡ የማይቻላቸውን ፡ የማይረባቸ
ውን ፡ የማይጠቅማቸውን ፡ በሰማይ ፡ ያሉ ፡ ከዋክብትን ፡

ከዋክብተ ፡ ሰማይ ፡ ዘኢበቍዖሙ ፡ ወእለ ፡ ኢይክሉ ፡
አድኅኖቶሙ ።

፲ እስመ ፡ እሙንቱሰ ፡ ኢይክሉ ፡ ውሂበ ፡ ወነ
ሢአ ፡ ኢየሐንጹ ፡ ወኢይነሥቱ ፡ ኢይተክሉ ፡ ወኢይ
ምሕዉ ፡ ኢያሜንዩ ፡ ወኢየሐሥሙ ፡ ኢያብዕሉ ፡ ወኢ
ያነድዩ ፡ ኢይቀትሉ ፡ ወኢየሐይዉ ፤ ኢላ ፡ ዳዕሙ ፡ ይከ
ውኑ ፡ ዕቅፍተ ፡ ለአስሕቶ ፡ ኢብዳን ።

፲፩ ዑቁኬ ፡ እንከ ፡ ኢያስሕቱክሙ ።

፲፪ አምላከ ፡ ሰላም ፡ የሀሉ ፡ ምስሌክሙ ፡ ወያ
ብርህ ፡ ጽልመተ ፡ ሕሊናክሙ ፡ ወፈሪሃ ፡ ስሙ ፡ ይደይ ፡
ውስተ ፡ ልብክሙ ፡ ታእምሩ ፡ ሕጋ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ።

፲፫ ወአንትሙሂ ፡ እንዘ ፡ ትረድኡኑ ፡ በጸሎት
ክሙ ፡ እስመ ፡ ጸሎተ ፡ ጻድቅ ፡ ትክል ፡ ወትረድዕ ፡ ወታ
ሰልጥ ፡ ወባቲ ፡ ተስፋ ፡ ሕይወት ፡ ዘለዓለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

## በእንተ ፡ ሕዝብ ፡ ቀዊመ ፡ ቅድመ ፡ ንጉሥ ።

፩ ወአንትሙኒ ፡ ሕዝብ ፡ ለምንት ፡ ዘኢትገ
ይሙ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በምንት ፡ ታመክንዩ ፡



የሚያመልኩ ፡ ለጨረቃና ፡ ለፀሐይ ፡ የሚሰግዱ ፡ እንጨት
ጠርበው ፡ ድንጋይ ፡ አለዝበው ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልኩ ፡
ሁሉ ፡ የተረገሙ ፡ ናቸው ።

፲ እሊህ ፡ ጣዖታት ፡ ሰነፎች ፡ ሰዎችን ፡ ለማሳት ፡
መሰናክል ፡ ይሆናሉ ፡ እንጂ ፡ መግደል ፡ ማዳን ፡ ድኃ ፡
ባለጸጋ ፡ ክፉ ፡ መልካም ፡ ማድረግ ፡ መትከል ፡ መንቀል ፡
ማነጽ ፡ ማፍረስ ፡ መስጠት ፡ መንሳት ፡ አይቻላቸውምና ፡
እሊህን ፡ ትታችሁ ፡ ሁሉን ፡ ማድረግ ፡ በሚቻለው ፡
በእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ እመኑ ።

፲፩ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንዳያስትዋችሁ ፡ ዕወቁ ።

፲፪ የፍቅር ፡ ያንድነት ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡
የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሥርዓቷን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ ስሙን ፡
መፍራትንም ፡ በልቡናችሁ ፡ ያሳድርባችሁ ዘንድ ፡
የሕሊናችሁንም ፡ ድንቁርና ፡ ያርቅላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከእና
ንተ ፡ ጋር ፤ በእናንተ ፡ አድሮባችሁ ፡ ይኑር ።

፲፫ እናንተም ፡ የጻድቅ ፡ ሰው ፡ ጸሎት ፡ የዘለ
ዓለም ሕይወት ፡ ለመውረስ ፡ አለኝታ ፡ ያለባት ፡
በመርዳት ፡ ግዳጅ ፡ የምትፈጽም ፡ ናትና ፡ በምትጸልዩት ፡
ጸሎት ፡ ሁሉ ፡ እያገዛችሁን ፡ እየረዳችሁን ፡ ይሁን ።

## ፲፭ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ ሕዝብ ፡ በሰማያዊ ፡ ንጉሥ ፡ ፊት ፡ መቆም ።

፩ እናንት ፡ ምእመናን ፡ ከሰኞ ፡ እስከ ፡ ቀዳሚት ፤ ድረስ
የተኛችሁት ፡ አልበቃችሁምን ፡ ንጽሕናን ፡ ይዛችሁ ፡

እመ ፡ ትቀውሙ ፡ ቅድሜሁ ፡ ለሰማያዊ ፡ ንጉሥ ፡ እስከ
ቀዳሚት ፡ ሰንበት ፡ ዘኖምክሙ ፡ ኢየአክለክሙኑ ።

፫ ወኢሐቲ ፡ ዕለት ፡ ሰንበተ ፡ ክርስቲያን ፡ በገ
ኃትክሙኑ ፡ ከመ ፡ ኢታክብርዋ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

በእንተ ፡ መሃይምናን ፡ እለ ፡ ፀቀቡ ፡ ሕጎ ።

፩ ወቤተ ፡ ክርስቲያንሂ ፡ ትነግሮ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ አብ ፡ እንዘ ፡ ትብል ፡ ነዮሙ ፡ ውሉድየ ፡ መሃይ
ምናን ፡ እለ ፡ ይትቀነዩ ፡ ለከ ፡ ኀቤየ ፡ ወትረ ፡ እንተ ፡
ጸብሐት ።

፪ ወያወሥአ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡
ለቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወይቤላ ፡ አማን ፡
መርዓትየ ፡ ሰመይኩኪ ፡ ወምስለ ፡ ማርያም ፡ እምየ ፡
አስተማሰልኩኪ ፡ እንተ ፡ ፆረተኒ ፡ በከርሣ ፡ ፱ተ ፡ አው
ራኀ ፡ ወበደምየ ፡ ቀደስኩኪ ፡ በዕፀ ፡ መስቀልየ ፡ ዓተ
ብኩኪ ፡ ወረሰይኩኪ ፡ ምስአለ ፡ ወምስጋደ ፡ ወመሥ
ተስርየ ፡ ኃጢአት ፡ ዙሉ ፡ ሰብእ ፡ ወሀብኩኪ ፡ ኪዳነ ፡
ዘለዓለም ።



በጸሎት ፡ ተወሰናችሁ ፡ በዕለተ ፡ ሰንበት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ አለመገሥገሳችሁ ፡ ለምንድር ፡ ነው ፡ እን
ዲህማ ፡ በጽርዓት ፡ እንኖራለን ፡ ትሉ ፡ ዘንድ ፡ ሰማያዊ ፡
ንጉሥ ፡ ክርስቶስ ፡ በጌትነት ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ በምን ፡
ምክንያት ፡ ከፍዳ ፡ እንድናለን ፡ ብላችሁ ፡ ታመካኛላችሁ ።

፫ አናከብርም ፡ ትሉማ ፡ ዘንድ ፡ የክርስቲያን ፡
ዕረፍት ፡ የምትሆን ፡ ዕለተ ፡ እሑድን ፡ የማታከብሯት ፡
አንዲት ፡ ቀን ፡ በዛችባችሁን ?

፲፯ኛ ፡ ምዕራፍ ።

የጌታን ፡ ሕግ ፡ ስለጠበቁ ፡ ምእመናን ።

፩ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ማልደው ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
ወደኔ ፡ እየመጡ ፡ በጾም ፡ በጸሎት ፡ በስግደት ፡ ተወስ
ነው ፡ ሳንተ ፡ የሚገዙ ፡ ልጆቼ ፡ ምእመናን ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ፡ ብላ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትነግረዋለች። አሁን ፡
እርሱ ፡ የማያውቅ ፡ እርስዋ ፡ የምትናገር ፡ ሁና ፡
አይደለም ፡ ለሰው ፡ በመሰለ ፡ ነገር ፡ መናገር ፡ ነው ፡
እንጂ ።

፪ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስም ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡
ኃጢአት ፡ ማሥተስረያ ፡ መስገጃ ፡ መለመኛ ፡ አደረግ
ሁሽ ፡ በደሜ ፡ አከበርሁሽ ፡ በተሰቀልሁበት ፡ ዕፀ ፡ መስ
ቀልም ፡ ባረክሁሽ ፡ ፱ ፡ ወር ፡ ከ፭ ፡ ቀን ፡ በማኅፀኗ ፡ በተ
ሸከመችኝ ፡ በእናቴ ፡ በማርያምም ፡ መሰልሁሽ ፡ በውነት ፡
ማደሪያየ ፡ አልሁሽ ፡ ብሎ ፡ ንዕድ ፡ ክብርት ፡ ለምትሆን ፡
ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡
ቃል ፡ ኪዳን ፡ ሰጠሁሽ ፡ አላት ፡ ።

፫ ወመላእክትየኒ ፡ እለ ፡ ይትቀነዩ ፡ ሊተ ፡ ወይ
ሴብሑኒ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፡ ቀትረ ፡ ወሰዓተ ፡ ሠርከ ፡
ወነግሀ ፡ ይሴብሑኒ ፡ ወየአጥኑኒ ፡ ዘእንበለ ፡ ጽርዓት ፡
ወሐኬት ፡ ወድካም ፡ ሑሪ ፡ አብዒዮሙ ፡ ውስተ ፡ ገነት ፡
ትፍሥሕት ፡ ኀበ ፡ ሀለዉ ፡ አበዊሆሙ ፡ ቀደምት ፡ ኀበ ፡
አልቦ ፡ ደዌ ፡ ወአልቦ ፡ ሕማም ፡ ኀበ ፡ ኢይመውቱ ፡
እምዝ ፡ ዳግመ ፡ ብሔረ ፡ ሕያዋን ።

፬ ወታበውዖሙ ፡ ቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ለእለ ፡ ይጸመድዋ ፡ ኵሎ ፡ ጊዜ ፡ ዘእንበለ ፡ ድካም ፡
ወሐኬት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

## በእንተ ፡ ሰሚዐ ፡ ቃሉ ፡ ለመድኃኒነ ።

፩ ንው ፡ አ ፡ ፍቁራንየ ፡ ንስማዕ ፡ ቃሎ ፡ ለመድ
ኃኒነ ፡ ዘይቤ ፡ በወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ ንዑ ፡ ኀቤየ ፡ ስሩኃን ፡
ወክቡዳን ፡ ፆር ፡ ወአነ ፡ አአርፈክሙ ።



፫ ማታና ፡ ጧት ፡ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ የሚያገ
ለግሉኝ በየሰዓቱ ፡ ፈጽመው ፡ የሚያመሰግኑኝ ፡ ምስጋና ፡
ከአፋቸው ፡ የማያቋርጥ ፡ መላእክትም ፡ ድካም ፡ ሳይኖ
ርባቸው ፡ ቸል ፡ ሳይሉ ፡ ያሚያጥኑሽ ፡ ሁለተኛ ፡
ሞት ፡ ወደሌለበት ፡ የቀድሞ ፡ አባቶቻቸው ፡ ወዳሉበት ፡
የሕያዋን ፡ አገር ፡ ወደምትሆን ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ወዳ
ለበት ፡ ገነት ፡ ወስደሽ ፡ አስገቢያቸው ፡ ይላታል ።

፬ ንዕድ ፡ ክብርት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ቸል ፡
ሳይሉ ፡ ድካም ፡ ሳይሰማቸው ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ጽምዕ ፡
እንደ ፡ በሬ ፡ ቅኑት ፡ እንደ ፡ ገበሬ ፡ ሁነው ፡ የሚያገለ
ግሏት ፡ ምእመናንን ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ታስ
ገባቸዋለች ፡ በቅንነት ፡ በሚገባ ፡ ያገለገለ ፡ ዋጋ ፡ ማግ
ኘቱን ፡ ያላገለገለ ፡ ግን ፡ ፍዳ ፡ መቀበሉን ፡ መናገር ፡ ነው ።

## ፲፱ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## የመድኃኒታችንን ፡ ቃል ፡ ስለመስማት ።

፩ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ የምትፋቀሩ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ የምትወዱ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚወዳችሁ ፡ ወን
ድሞቻችን ፡ ሆይ ፡ ከአላ ፡ ሁያን ፡ ነገሥታት ፡ ከአላው
ያን ፡ መኳንንት ፡ እሳት ፡ ስለት ፡ የተቀበላችሁ ፡ እጸበ ፡
ገዳም ፡ ድምፀ ፡ አራዊት ፡ ጸብአ ፡ አጋንንትን ፡ በመታ
ገስ ፡ የደከማችሁ ፡ የከበደ ፡ ቀንበር ፡ (መከራ) የተሸከ
ማችሁ ፡ ዕረፍተ ፡ ነፍስን ፡ ሰጥቼ ፡ አሳርፋችሁ ፡ ዘንድ ፡
በክብር ፡ ወደኔ ፡ ኑ ብሎ ፡ መድኃኒታችን ፡ ኢየ
ሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በከበረ ፡ ወንጌል ፡ የተናገረውን ፡ የከ
በረ ፡ ነገሩን ፡ እንሰማ ፡ ዘንድ ፡ ኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

### በእንተ ፡ እለ ፡ ኖሙ ፡ ዘቢጠ ፡ እንግድዓ ።

፩ ወሶበ ፡ ትበውዑ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያ
ለምንት ፡ ትጐድዑ ፡ እንግድዓክሙ ፡ ከመ ፡ አረ
ውያን ፡ ወመጸብሐን ፤ ወውእቶሙሰ ፡ ኃጕሉ ፡ እ
ቶሙ ።

፪ ወአንተሰ ፡ ሶበ ፡ ትጼሊ ፡ ወትጸውም ፡ ቅባዕ
ርእሰከ ፡ ወተሐፀብ ፡ ገጸከ ፡ ከመ ፡ ኢታስተርኢ ፡ ለሰብእ
ከመ ፡ ጾምከ ።

፫ ጸሊ ፡ ለአቡከ ፡ በኅቡዕ ።

፬ ወአቡከ ፡ ዘይሬእየከ ፡ የአሥየከ ክሡተ ።

፭ ወኢንተሰ ፡ ሶበ ፡ ትጼሊ ፡ ባዕ ፡ ቤተከ
ወዕጹ ፡ ኖኃተከ ፡ ወዘንተ ፡ ዘይቤለከ ፡ ኢኮ ፡ ኖኃተ
ቤትከ ፡ አላ ፡ እንዘ ፡ ያረምም ፡ አፉከ ፡ ወአዕይንቲከ
እንዘ ፡ ድኑናት ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ወአዕይንተ ፡ ልብከ
ወአዕዳዊከ ፡ ስፉሓት ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ።



## ፲፰ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### ስለ ፡ ሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ደረትን ፡ መድቃት ፤

፩ ወደቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በምትገቡበት ፡ ጊዜ
ስለሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ዋጋቸውን ፡ እንዳጡ ፡ እንደ ፡ ጸሐ
ፍት ፡ ፈሪሳውያን ፤ እንደ ፡ አረማውያንም ፡ ደረታች
ሁን ፡ እየደቃችሁ ፡ ለምን ፡ ትገባላችሁ ።

፪ መንፈሳዊ ፡ አርበኛ ፡ የምትሆን ፡ አንተ ፡ ግን ፡
በጾምህ ፡ በጸለይህ ፡ ጊዜ ፡ ስትጾም ፡ ስትጸልይ ፡ እንደ ፡
ጾምህ ፡ ሰው ፡ እንዳያውቅብህ ፡ ራስህን ፡ ቅባ ፡ ፊትህን፡
ታጠብ ፡ የተቀባ ፡ የታጠበ ፡ እንዳይታወቅበት ፡ አይታ
ወቅብህ ፡ ሲል ፡ ነው ።

፫ ተሠውረህ ፡ ስትጸልይ ፡ ተሠውሮ ፡ ወደሚ
ያይህ ፡ ወደ ፡ ሰማያዊ ፡ አባትህ ፡ ጸልይ ።

፬ ተሠውረህ ፡ ስትጸልይ ፡ ተሠውሮ ፡ የሚያይህ ፡
ሰማያዊ ፡ አባትህ ፡ ገልጾ ፡ ዋጋህን ፡ ይሰጥሃል ።

፭ አንተ ፡ ግን ፡ ስትጸልይ ፡ በምትጸልይበት ፡ ጊዜ
ከቤትህ ፡ ገብተህ ፡ በርህን ፡ ዘግተህ ፡ ጸልይ ፡ ያለህ ፡
የቤትህን ፡ በር ፡ ዘግተህ ፡ አዕይንተ ፡ ሥጋህ ፡ ምድር ፡
ምድር ፡ እየተመለከቱ ፡ እንደበቶኽ ህ ፡ ከመናገር ፡ ዝም ፡
ብለው ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ በአንቃዕድዎ ፡ አዕይንት ፡
በሰፊሐ ፡ አዕዳው ፡ በተዘክሮ ፡ ሕሊና ፡ በአዕይንተ ፡
ልቡና ፡ ሁነህ ፡ ሰማያዊ ፡ ነገር ፡ እያሰብሕ ፡ ጸልይ ፡ ሲል ፡
ነው ።

፮ ስእል ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምቅድመ ፡ ሕሊና ፡ ኵሉ ፡ የአምር ፡ ወእምቅድመ ፡ ሕሊና ፡ ይፈትን ።

፯ ወዘእንበለ ፡ ንስእሎ ፡ ይሁብ ፡ ፍትወተነ ፡ ዘእምፈቃዱ ።

፰ ኢሰማዕክሙኑ ፡ ዘይቤ ፡ በወንጌል ፡ ቅዱስ ፡
፪ ዕደው ፡ ዓርጉ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይጸልዩ ፡
፩ ፈሪሳዊ ፡ ወካልዑ ፡ መጸብሐዊ ።

፱ ወፈሪሳዊ ፡ ጸለየ ፡ ወይቤ ፡ በትዕቢቱ ፡ ወበግዘፈተ ፡ ልቡ ፡ እእኵተከ ፡ እግዚኦ ፡ ወኢ ፡ ረሰይከኒ ፡ ከመ ፡ ባዕዳን ፡ ሰብእ ፡ ሐያድያን ፡ ወዓማጽያን ፡ ወእለ ፡ የሐውሩ ፡ ኀበ ፡ ብእሲተ ፡ ብእሲ ፡ ወኢከመ ፡ ዝንቱ ፡ መጸብሐዊ ።

፲ ወእጸውም ፡ ካዕበተ ፡ ለለሰንበት ።

፲፩ ወአበውእ ፡ ዓሥራተ ፡ እደ ፡ ሁ ፡ ለኵሉ ፡ ዘአጥረይኩ ።

፲፪ ወመጸብሐዊሰ ፡ ቆመ ፡ እምርኁቅ ፡ አንዘ ፡ ድኅን ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ አዕይንተ ፡ ልቡ ፡ ወአደዊሁ ፡ ስፉሓት ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፡ ስረይ ፡ ሊተ ፡ ለኃጥእ ።

፮ የሚደረገውን ፡ ከመደረጉ ፡ የሚታሰበውን ፡ ከመታሰቡ ፡ አስቀድሞ ፡ ወደሚያውቅ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸልይ ።

፯ የምንለምነውን ፡ ሳንለምነው ፡ አስቀድሞ ፡ እንዲያሻን ፡ አውቆ ፡ ወደሚሰጠን ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢመልክት ።

፰ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ አንዱ ፡ ቀራጭ ፡ ሁለተኛውም ፡ ፈሪሳዊ ፡ ሊጸልዩ ፡ ወደቤተ ፡ መቅደስ ፡ ገቡ ፡ ብሎ ፡ ጌታ ፡ በከበረ ፡ ወንጌል ፡ የተናገረውን ፡ አልሰማችሁምን ?

፱ ፈሪሳዊም ፡ በልቡናው ፡ ድንቁርና ፡ በመታበይ ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ የበደልን ፡ የቅሚያን ፡ ሥራ ፡ እንደሚሠሩ ፡ እንደ ፡ ሌሎቹ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ጐልማሳ ሚስት እንደሚሄዱ ፡ ይልቁንም ፡ እንደዚህ ፡ እንደ ፡ ቀራጭ ፡ ያላደረግኸኝ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ጸለየ ።

፲ ዳግመኛም ፡ ከሳምንት ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ እጾማለሁ ።

፲፩ ከገንዘቤ ፡ ሁሉም ፡ ከዐሥር ፡ አንድ ፡ እሥራት ፡ አወጣለሁ ፡ ሳያወጣ ፡ እግዚአብሔር ፡ የማይወደውን ፡ ሐሰት ፡ ነገር ፡ ተናገረ ።

፲፪ ቀራጩ ፡ ግን ፡ ርቆ ፡ ቆሞ ፡ ዓይኑ ፡ ሥጋው ፡ በእምድር ፡ ምድር ፡ እየተመለከተ ፡ በስፉሕ ፡ እጆቹ ፡ አቤቱ ፡ የኔን ፡ ንቃዕድዎ ፡ ሕሊና ፡ ሰማያዊ ፡ ነገር ፡ አስቦ ፡ አቤቱ ፡ የኔን ፡ የኃጥእን ፡ ኃጢአት ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አመለከተ ።

፲፫ እብለክሙ ፡ ዓተወ ፡ ቤቶ ፡ እንዘ ፡ ይጸድቅ ፡
ዝንቱ ፡ እምዝክቱ ።

፲፬ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ዘዓልአለ ፡ ርእሶ ፡ የኅሥር ፡
ወዘአትሐተ ፡ ርእሶ ፡ ይከብር ።

፲፭ ወእምከመ ፡ ቦአ ፡ ትዕቢት ፡ ውስተ ፡ ልቡ ፡
ለሰብእ ፡ ፍጡነ ፡ ይከውን ፡ ድቀቱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

## በእንተ ፡ ፍቅረ ፡ ቢጽ ።

፩ ወእምኵሉሰ ፡ ዘይቀድም ፡ ተፋቀሩ ፡ በበይና
ቲክሙ ፡ እስመ ፡ ተፋቅሮ፡ይደፍኖን ፡ ወይደመስሶን
ለኵሎን ፡ ኃጣውእ ።

፪ ኢስማዕክኑ ፡ ዘይቤ ፡ ሐዋርያ ፡ ወእመሰ ፡ ዘት
ሬኢ ፡ ቢጸከ ፡ ዘኢታፈቅር ፡ እፎኑ ፡ ትትክል ፡ አፍቅሮቶ፡
ለእግዚአብሔር ዘኢትሬኢ ።

፫ አፍቅሩ ፡ ጸላእተክሙ ።



፲፫ ከፈሪሳዊው ፡ ይልቅ ፡ ቀራጩ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ዘንድ ፡ ከብሮ ተመስግኖ ፡ ተመለሰ ፡ ብዬ ፡
እነግራችኋለሁ ።

፲፬ እራሱን ፡ ያከበረ ፡ ይዋረዳልና ፡ ትዕቢትን ፡
ከናንተ ፡ አርቁ ፡ ራሱን ፡ ያዋረደ ፡ ይከብራልና ፡ ትሕት
ናን ፡ ገንዘብ ፡ አድርጉ ፡ ብሎ ፡ ጌታ ፡ በወንጌል ፡ የተና
ገረውን ፡ አልተመለከታችሁም ።

፲፭ ትዕቢት ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡ ያደረ ፡ እንደሆነ ፡
ፈጥኖ ፡ ወደ ፡ ጽኑዕ ፡ ገደል ፡ ክህደት ፡ ይወድቃልና ፡
ከትዕቢት ፡ ተጠበቁ ።

## ፲፱ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ወንድምን ፡ ስለ ፡ መውደድ ።

፩ ፍቅር ፡ ኃጣውእን ፡ ሁሉ ፡ እንዲሠሩ ፡ አያደር
ግምና ፡ ቢሠሩም ፡ በፍዳ ፡ እንዲያስዚዙ ፡ አያደርግምና ፡
ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አስቀድሞ ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ ፍቅርን ፡
ገንዘብ ፡ አድርጉ ።

፪ የምታየው ፡ ወንድምህን ፡ ሳትወድ ፡ የማታየ
ውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እወደዋለሁ ፡ እንደምን ፡ ትላለህ ፡
ይኸማ ፡ ፍዳ ፡ ይሆንብህ ፡ የለም ፡ ብሎ ፡ ሐዋርያው ፡ የተና
ገረውን ፡ አለሰማህም ።

፫ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ እንድትባሉ ፡ ጠላ
ቶቻችሁን ፡ ውደዱ ።

፬ ወደኃርዎሙ ፡ ለእለ ፡ ይረግሙክሙ ።

፭ ደኃሩ ፡ ወኢትርግሙ ።

፮ ወዘእንበለ ፡ ይዕርብ ፡ ፀሐይ ፡ አቁርሩ ፡ መዓ
ተክሙ ።

፯ መነሂ ፡ እስከ ፡ ለሰይጣን ፡ ጥቀ ፡ ኢትርግሙ ፡
እስመ ፡ ቀዲሙሰ ፡ መልአከ ፡ ኪዳኑ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ውእቱ ።

፰ ለእመ ፡ ርኅበ ፡ ጸላዒከ ፡ አብልዖ ፡ ወለእመ ፡
ጸምዓ ፡ አስትዮ ።

፱ ወለእመ ፡ ገበርከ ፡ ዘንተ ፡ ኢፍሐመ ፡ እሳት ፡
ታስተጋብእ ፡ ዲበ ፡ ርእሱ ።

፲ ማፆ ፡ ለእኩይ ፡ በገቢረ ፡ ሠናይ ።

፲፩ ወልድየ ፡ ኢትሀብ ፡ ምክንያተ ፡ ለሰብእ ፡
በዘይረግመከ ።

፲፪ ወእመሰ ፡ ረገመከ ፡ በምረት ፡ ልቡ ፡ ፍጡነ ፡
ይሰምዖ ፡ ፈጣሪሁ ።

፲፫ ወካዕበ ፡ ይቤ ፡ ወልድየ ፡ ኢታስተዓፅብ ፡
ተግሣፀ ፡ እግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ለዘያፈቅር ፡ ይጌሥፆ ፡
እግዚአብሔር ።



፬ የሚረግሙዋችሁንም ፡ መርቋቸው ፡ ከሀገራችሁ
አያውጣችሁ ፡ እያላችሁ ።

፭ መርቁ ፡ እንጂ ፡ አትርገሙ ።

፮ ብትጣሉም ፡ ፀሐይ ፡ ሳይገባ ፡ ታረቁ ፡ ሳት
ታረቁ ፡ አትደሩ ።

፯ እስቀድሞ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባለሟል ፡ ነበ
ርና ፡ ሌላውስ ፡ ይቅርና ፡ ሰይጣን ፡ ሳይቀር ፡ ማንም ፡
ማንን ፡ አትርገሙ ።

፰ ጠላትህ ፡ ቢጠማ ፡ አጠጣው፡ ቢራብ፡ አብላው።

፱ ይህን ፡ ብታደርግ ፡ እፍሐመ ፡ ፍቅርን ፡ በሰ
ውነቱ ፡ ታሳድርበታለህ ።

፲ ክፉውን ፡ ሰው ፡ በበጎ ፡ ግብር፡ድል ፡ ንሣው።

፲፩ ፤ ልጄ ፡ በሚረግምህ ፡ ገንዘብ ፡ ይረግምህ ፡
ዘንድ ፡ የምትረገምበት ፡ ምክንያት ፡ ለሰው ፡ አትስጥ ።

፲፪ በልቡናው ፡ ምርር ፡ ብሎ ፡ የረገመህ ፡ እን
ደሆነ ፡ ፈጣሪው ፈጥኖ ፡ ልመናውን ፡ ይሰማዋልና ፡
እንዳትቀሠፍ ።

፲፫ ልጄ ፡ አባት ፡ ልጁን ፡ እንዲሠራው ፡ እንዲ
ቀጣው ፤ እግዚአብሔርም ፡ የወደደውን ፡ ሰው ፡ በመከራ
ይሠራዋል ፡ ይቀጠዋልና ፡ መከራ ፡ አመጣብኝ ፡ ብለህ
እግዚአብሔር፡ ያመጣብህን ፡ መከራ ፡ ዕጹብ ፡ ዕጹብ ፡
አትበል ፡ አትመረር ፡ አትሰልች ፡ አትሰቀቅ ።

፲፩ ወእመሰ ፡ ኢገሠፅክሙ ፡ አንደበራ ፡ አንትሙ
ዘአልቦ ፡ ልብ ፡ ወኢኮንክሙ ፡ ውሉደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

## በእንተ ፡ ጸሊዓ ፡ እግዚአብሔር ።

፩ ወለምንትኑ ፡ ትጸልኡኒ ፡ ኪያየ ፡ ይቤ እግ
ዚአብሔር ፡ ዘኢልሐቁክሙ ፡ ወዘፈጠርኩክሙ ፡ በውስተ፡
ከርሠ ፡ እምክሙ ፡ ሐፀንኩክሙ ።

፪ ወእምነ ፡ አበዊክሙሂ ፡ አፈድፈድክሙ ፡
ገቢረ እኪት ላዕሌየ ።

፫ ወሶበ ፡ ተሐምሙ ፡ ፈውሰነ ፡ ትብሉኒ ፡ እምዝ
ሕማም ።

፬ ወአነኒ ፡ አአምረክሙ ፡ ከመ ፡ ኢትገብኡ ፡
ውስተ ፡ ንስሐ ።

፭ ወአነኒ ፡ አፈደፍድ ፡ ምክዕቢተ ፡ ሕማመ ።

፮ ወርኁባኒክሙ ፡ አጽገብኩክሙ ፡ ወጽሙአ
ኒክሙ ፡ አርወይኩክሙ ፡ ወዕሩቃኒክሙ ፡ ኢልበስኩክሙ
በሠናይ ፡ አዕበይኩክሙ ፡ ሠናየ ፡ ሰብአ ፡ ረሰይኩክሙ።

፯ መላእክተ ፡ ፈጠርኩ ፡ በእንቲአክሙ ።



በመከራ ፡ ካልሠሯችሁ ፡ ካልቀጧችሁ ፡ ግን
፲፩ ዕውቀት ፡ እንደሌናው ፡ ሰው ፡ ባዕድ ፡ መሆናችሁ ፡
ነውና ፡ ልጅ ፡ አትባሉም ።

## ፭ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## እግዚአብሔርን ፡ ስለ ፡ መጥላት ።

፩ ከናታችሁ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ ፈጥሬ ፡ ያሳደ
ግኋችሁ ፡ ከፍጹም ፡ መዓርግ ፡ ያደረስኋችሁ ፡ እኔን፡ የጠ
ላችሁበት ፡ ምክንያት ፡ ምንድር፡ ነው፡ ለምን ጠላችሁኝ ፡
አለ ፡ እግዚአብሔር ።

፪ ከአባቶቻችሁ ፡ ይልቅ ፡ በኔ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ አበ
ዛችሁብኝ ።

፫ በታመማችሁ ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ በሽታችን ፡ አድ
ነን ፡ ትሉኛላችሁ ።

፬ እኔም ፡ በንስሓ ፡ ወደኔ ፡ እንዳትመለሱ ፡
አውቃለሁና ።

፭ መከራውን ፡ መቶ ፡ እጽፍ ፡ ድርብ ፡ አድርጌ፡
አብዝቼ ፡ አመጣባችኋለሁ ።

፮ ብትራቡ አብልቼ ፡ ብትጠሙ ፡ አጠጥቼ ፡
ብትታረዙ ፡ አለበስኋችሁ እንዲህ ፡ አድርጌ፡ በፍጹም፡
ክብር፡ አክብሬ፡ በበጎ ማሳደግ አሳደግኋችሁ፡ ያማረ፡ ባለአ
እምሮ ፡ ሰውን ፡ አድርጌ ፡ የፈጠርኋችሁ ።

፯ ስለናንተ ፡ መላእክትን ፡ የፈጠርሁ ።

፰ ሰማየ ፡ ፈጠርኩ ፡ ከመ ፡ ታውርድ ፡ ዝናመ ፡ በእን ቲአክሙ ።

፱ ወለምድርኒ ፡ አዘዝክዋ ፡ ከመ ፡ ታውጽእ ለክሙ ፡ ፍሬያተ ፡ ዘዘዚአሁ ፡ ዘአልቦ ፡ ኍልቍ ፡ በበዘመዱ ፡ በእንቲአክሙ ።

፲ ፀሐየ ፡ ፈጠርኩ ፡ ከመ ፡ ያብርህ ፡ በመዓልት ፡ ወርኃ ፡ ወከዋክብተ ፡ ከመ ፡ ያብርሁ ፡ በሌሊት ፡ በእን ቲአክሙ ።

፲፩ ኢድባረ ፡ ወኢጨግረ ፡ ዕፀ ፡ ወአዕባነ ፡ ባሕረ ፡ ወአፍላገ ፡ አንቅዕተ ፡ ወቀላያተ ፡ ዓሣተ ፡ ወአናምርተ ፡ ወኵሎ ፡ ተሐዋስያነ ፡ ዘቦ ፡ እግር ፡ ወነፍስ ፡ ወዘቦ ፡ ክንፍ ፡ ዘይሰርር ፡ ወኵሎ ፡ አራዊተ ፡ ጽኑዓነ ፡ በእንቲአክሙ ፡ ፈጠርኩ ።

፲፪ ወእመኒ ፡ ዘየሐውር ፡ በክበዱ ።

፲፫ ወዘንተ ፡ ፈጠርኩ ፡ በእንቲአክሙ ፡ ለእመ ርኅብኩኑ ፡ ከመ ፡ ታብልዑኒ ፡ ወእመዓረቁኑ ፡ ከመ ፡ ታልብሱኒ ፡ ወለእመ ፡ ደወይኩኒ ፡ ከመ ፡ ትሬውሱኒ ።



፰ ለእናንተ ፡ ዝናም ፡ ለዘር ፡ ጠል ፡ ለመከር ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ እናንተ ፡ ሰማይን ፡ ፈጠርሁ ።

፱ ምድርም ፡ ስለናንተ ፡ በየወገኑ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሚሆኑ ፡ ፍሬያትን ፡ ታፈራ ፡ ዘንድ ፡ ፈጥሬ ፡ አዘዝኋት ።

፲ ስለናንተ ፡ ፀሐይ ፡ በመዓልት ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ፣ በሌሊትም ፡ ከዋክብትና ፡ ጨረቃን ፡ ያበሩ ፡ ዘንድ ፡ የፈጠርሁ ።

፲፩ ድካም ፡ የሌላቸው ፡ ጽኑዓን ፡ አራዊትን ሁሉ በክንፍ ፡ የሚበሩ ፡ በእግር ፡ የሚሽከረከሩ ፡ ደመ ፡ ነፍስ ያላቸው ፡ ተሐዋስያን ፡ ሁሉ ፡ ዓሣ ፡ አንበሬ ፡ አዞ ፡ ጉማሬውን ፡ አናምርትንም ፡ ጥልቁን ፡ ባሕር ፡ ምንጩን ፡ ፈሳሹን ፡ ውሃ ፡ ጥልቅ ፡ ያልሆነውን ፡ ባሕር ፡ ድንጋዮቹን ፤ እንጨቶቹን ፡ ተራራውን ፡ ኮረብታውን ፡ ሁሉ ፡ ስለናንተ ፡ አንክሮ ፡ ለተዘክሮ ፡ ፈጠርሁ ።

፲፪ በደረቱ ፡ እየተሳበ ፡ የሚሄደውን ፡ አውሬ ፡ ሁሉ ፡ የፈጠርሁላችሁ ።

፲፫ ይህን ፡ ሁሉ ፡ የፈጠርሁላችሁ ፡ ብራብ ፡ እንድታበሉኝ ፡ ብጠማ ፡ ልታጠጡኝ ፡ ብታረዝ ፡ ልታለብሱኝ ፡ ብታመም ፡ ልትፈውሱኝ ፡ ነው ፡ አንክሮውን ፡ ልትተዘክሮውን ፡ እያሰባችሁ ፡ ሕጌን ፡ አምልኮቴን ፡ ልትጠብቁ ፤ ነው ፡ እንጂ ፡ እኔማ ፡ ምን ፡ ዕዳዬ ፡ መከራውን ፡ ለምትቀበሉ ፡ ለእናንተ ፡ ይባስ ፡ እንጂ ።

፲፬ ወዘንተ ፡ ኵሎ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚእን ፡ እሙን ፡ ውእቱ ፡ ወኢኮነ ፡ ሐሰተ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

## በእንተ ፡ ርደተ ፡ መና ።

፩ ወለአበዊክሙሰ ፡ ሴሰይክዎሙ ፡ ፵ ፡ ዓመተ ፡ በገዳም፡ መና፡ እምሰማይ፡ አውረድኩ፡ ሎሙ፡ ወአዝነምኩ፡ ሎሙ ፡ ሥጋ ፡ ከመ ፡ መሬት ።

፪ መዓልተ ፡ ፀሐይ ፡ ኢያውዕዮሙ ፡ ወሌሊተ ፡ በብርሃነ ፡ እሳት ፡ መራሕክዎሙ ።

፫ ሐሊበ ፡ ወመዓረ ፡ ሴሰይክዎሙ ።

፬ እምኅምዝ ፡ ወእምዕጉስታር ፡ ይመርሮሙ ፡ ምግባራ ፡ ለጽድቅ ።

፭ እመዓር ፡ ወሦከር ፡ ይጥእሞሙ ፡ ምግባራ ፡ ለኃጢ አት ።



፲፬ ጌታችን ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ የተናገረ ፡ እውነት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሐሰት ፡ አይደለም ፡ የሐሰት ፡ ነቅዑ ፡ መገኛው ፡ ፍጡር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፈጣሪ ፡ ነውን ? እስኪ ፡ እናንተም ፡ በዓይነ ፡ ልቡናችሁ ፡ አስተውሉት ።

## ፳፩ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለመና ፡ መውረድ ።

፩ አባቶቻችሁንም ፡ ሥጋውን ፡ እንደ ፡ ጽንኩል አድርጌ ፡ አዘነምሁላቸው ፡ መና ፡ ከደመና ፡ አውርጄ ፡ ዓርባ ፡ ዘመን ፡ መገብኋቸው ።

፪ በመዓልት ፡ ዋዕየ ፡ ፀሐይ ፡ እንዳያቃጥላቸው፡ በሌሊት፡ በብርሃነ ፡ እሳት፡ መርቼ ፡ ከግብፅ፡ አወጣኋቸው።

፫ ማርና ፡ ወተትም ፡ መገብኋቸው ።

፬ እውነተኛ ፡ የትሩፋት ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ከዕባብ፡ መርዝ ፡ ከእሬትም ፡ ይልቅ ፡ ይመራቸዋል ፡ አለ ፡ እግዚ አብሔርን ፡ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ የተከናወነ ፡ ሥራ ፡ መሥ ራት ፡ ትተው ፡ የሚያሳዝን ፡ ጠማማ ፡ ሥራ ፡ ይሠራሉ ፡ ኋላ ፡ ፍዳ ፡ ተቀብሎ ፡ ለማዘን ።

፭ ከሸንኰርና ፡ ከማር ፡ ይልቅ ፡ የኃጢአት ፡ ሥራ ይጣፍጣቸዋል ፡ አለ ፡ ገነት ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ የሚ ያገባ ፡ ሥራ ፡ ትተው ፡ ወደገሃነም ፡ የሚያወርድ ፡ ሥራ ይሠራሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

### በእንተ ፡ ሞተ ፡ እግዚእነ ፡

፩ ወአንሰ ፡ ሞተ ፡ ጥዕምኩ ፡ በእንቲአሆሙ ፡
ዘአልብየ ፡ አበሳ ፡ ወኃጢአት ።

፪ አክሊለ ፡ ዘሦክ ፡ ተቀጸልኩ ፡ ከለሜዳ ፡ ዘለይ፡
ለበስኩ ፡ ብሂአ ፡ ምስለ ፡ ሐሞት ፡ ከርቤ ፡ በሰፍነግ ፡
ሰተይኩ ።

፫ ምራቀ ፡ ርኩሳን ፡ ተፍዑ ፡ ውስተ ፡ ገጽየ ።

፬ ከመ ፡ ገብር ፡ ተጸፋዕኩ ።

፭ ወቅትራተ ፡ ዘብርት ፡ ተዓገሥኩ ፡ በእንቲአ
ክሙ ።

፮ አመ ፡ ረገዙኒ ፡ ገቦየ፡ በኲናት ፡ ዘንተ ፡ ኵሎ ፡
ኮንኩ ፡ ወተዓገሥኩ ፡ በእንቲአክሙ ።

፯ ወሶበ ፡ ተሐምሙ ፡ ተኃዝኑ ፡ ወትበክዩ ፡ ወታ
ውኅዙ ፡ አንብዓ ፡ መሪረ ፡ ወትብሉኒ ፡ መሐረነ ።

፰ ወአንሰ ፡ እጸብጠክሙ ፡ ከመ ፡ ዖፍ ፡ ዘተእኅዘ፡
በመሥገርት ፡ ወከማሁ ፡ አንትሙኒ ፡ እምከመ ፡ አኃዝ



## ፳፪ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### ስለ ፡ ጌታችን ፡ ሞት ።

፩ እኔ ፡ ግን ፡ ስለነሱ ፡ በነሱ ፡ ምክንያት ፡ ኃጢ
አት ፡ ሳልሠራ ፡ የምሞትበት ፡ ዕዳ ፡ በደል ፡ ሳይኖርብኝ
ፍጥረትን ፡ ሁሉ ፡ ከፍዳ ፡ አድኖ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡
ሞትን ፡ ተቀበልሁ ፡ (ሞትሁ) ።
፪ የብረት ፡ እሾህ ፡ ያለበት ፡ አክሊል ፡ በራሴ ፡
ላይ ፡ ደፉብኝ ፡ ቀይ ፡ ግምጃም ፡ ለበስሁ ፡ ከርቤ ፡ የተቀላ
ቀለውን ፡ ሐሞት ፡ በጁህ ፡ ባዘቶ ፡ ጠጣሁ ።
፫ ርኩሳን ፡ አይሁድ ፡ ምራቃቸውን ፡ በፊቴ ፡
ላይ ፡ ጢቅ ፡ አሉብኝ ።

፬ እንደ ፡ ባሪያ ፡ ፊቴን ፡ ተጸፋሁ ።

፭ ስለናንተ ፡ እንደ ፡ መጋዝ ፡ የሚቆራርጥ ፡ የብ
ረት ፡ መታጠቂያ ፡ ታጥቄ ፡ ሥቃዬን ፡ ሁሉ ፡ ታግሼ ፡ ተቀ
በልሁ ።

፮ አይሁድ ፡ ጐኔን ፡ በጦር ፡ በወጉኝ ፡ ጊዜ ፡
ስለናንተ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ሥቃይ ፡ ታግሼ ፡ ተቀበልሁ ።

፯ መከራ ፡ ባገኛችሁ ፡ ጊዜ ፡በማልቀስ ፡ መሪር፡
ዕንባን ፡ እያጐረፋችሁ ፡ ማረን ፡ ትሉኛላችሁ ፡ የሚማር፡
በመጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ የፈጸመ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
ማናቸውም ሕግ ፡ አፍራሽ ፡ሁሉ ፡ ይማራልን ።

፰ እኔ ፡ ግን ፡ በወጥመድ ፡ እንደ ፡ ተያዘች፡ ወፍ፡
በእደ ፡ መዓቴ ፡ አስጨንቄ ፡ እይዛችኋለሁ ፡ እናንተም ፡

ኵክሙ ፡ ወዐበጥኩክሙ ፡ ኢትክሉ ፡ አምሥጦ ፡
እምእዴየ ።

፱ ወሶበ ፡ ትርኅቡ ፡ ትዜከሩኒ ፡ ወሶበ ፡ ትጸግቡ፡
ትረስዑኒ ።

፲ ወትብሉ ፡ መሐረነ ፡ ወኢይሰምዐክሙ ፡ ጸሎ
ትክሙ ።

፲፩ እምከመ ፡ ጥዒክሙ ፡ ታፈደፍዱ ፡ ገቢረ ፡
እኪት ፡ ወትረስዑኒ ።

፲፪ ስምዑ ፡ ፍቁራንየ ፡ አንሰ ፡ ሶበ ፡ እሬኢ ፡ ዘት
ሰርሑ ፡ ወታሠረግዉ ፡ አጽሕርተ ፡ ቤትክሙ ፡ ከመ ፡
ዘትነብሩ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ።

፲፫ ዮምሰኬ ፡ ሰብእ ፡ ወጌሠመ ፡ መሬት ።



በወጥመድ ፡ የተያዘች ፡ ወፍ ፡ ማምለጥ ፡ እንዳይቻላት ፡
እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ ይገፔ ፡ የጨበጥኋችሁ ፡ እንደሆነ ፡
ከእደ ፡ መዓቴ ፡ ማምለጥ ፡ አይቻላችሁም ።

፱ በተራባችሁ ፡ በተጠማችሁ ፡ ጊዜ ፡ አብላን ፡
አጠጣን ፡ እያላችሁ ፡ በዚህ ፡ ምክንያት ፡ ታስቡኛላችሁ፡
በልታችሁ ፡ ጠጥታችሁ ፡ በጠገባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ትዘ
ነጉኛላችሁ ፡ አታስቡኝም ።

፲ ማረን ፡ ይቅር ፡ በለን ፡ እያላችሁ ፡ ትለምኑኛ
ላችሁ ፡ እኔም ፡ የልባችሁን ፡ ክፋት ፡ ጥመት ፡ አውቄ
ልመናችሁን ፡ አልቀበለውም ።

፲፩ ጤና ፡ ያገኛችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እኔን ፡ እረ
ስታችሁ ፡ አብዝታችሁ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ትሠራላችሁ ።

፲፪ ወዳጆቼ ፡ የምነግራችሁን ፡ ነገሬን ፡ ስሙ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደምትኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ጥቂት ፡ ሰዓት ፡
የምትቀመጡበትን ፡ እልፍኝ ፡ አዳራሽ ፡ በወርቅ ፡ በዕ
ንቍ ፡ ፈርጥ ፡ አስጌጣችሁ ፡ ለመሥራት ፡ ስትደክሙ ፡
ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ የሚያልፈውን ፡ ቤት ፡ ትተው ፡ የማያል
ፈውን ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ ይመስል ፡ እንዲህን ፡ ድንቁርና
ጸንቶባቸዋልን ፡ ብዬ ፡ ድንቁርናችሁን ፡ አደንቃለሁ ።

፲፫ ነገ ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ መሬት ፡ ናችሁ ፡
እንጂ ፡ ዛሬማ ፡ ዋጋው ፡ ውድ ፡ የሆነውን ፡ ከሐር ከወ
ርቅ ፡ የተሠራ ፡ ልብስ ፡ ለብሳችሁ ፡ አምማችሁ ፡ ጠም
ጥማችሁ ፡ ሰማይ ፡ ሰማይ ፡ እየተመለከታችሁ ፡ ስትሄዱ፡
ባለአእምሮ ፡ ሰው ፡ ትመስላላችሁ ።

፲፬ አንትሙ ፡ ዕጼ ፡ ዘይጸንሐክሙ ፡ ነደ ፡ እሳት
ከመ ፡ ይጸንሖ ፡ አንበሳ ፡ ለላህም ፡ በውስተ ፡ ግብ ፡
ከማሁ ፡ ሀሎ ፡ ይጸንሓክሙ ፡ ግበ ፡ እሳት ፡ ዘኢይጠፍእ ።

፲፭ ወእጽሕቅ ፡ በእንቲአክሙ ።

፲፮ ወእንዘ ፡ ሀሎክሙ ፡ በቅድሜየ ፡ ለምንትኑ ፡
ትሠርሑ ፡ አብያተ ፡ በዝየ ፡ እስመ ፡ ኢተአምሩ ፡ ጊዜ ፡
ይመጽእ ፡ ሐዳስ ፡ በዓለ ፡ ቤት ።

፲፯ አንትሙኒ ፡ ኦ ፡ ደቂቀ ፡ ፳ኤል ፡ ጽኑዓን ፡
ልብ ፡ ወግዙፋን ፡ ክሣድ ፡ ወለምንትኑ ፡ ኢትዜከሩ ፡
ዕለተ ፡ ሞትክሙ ።

፲፰ ወእምኔክሙሰ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡ ይኄይሱ
ክሙ ፡ ወኢይወርዱ ፡ ውስተ ፡ መሥገርት ፡ ወይትዓቀቡ ።

፲፱ ወአንትሙሰ ፡ እንዘ ፡ ትሬእዩ ፡ በአዕይንቲ
ቲክሙ ፡ ወእንዘ ፡ ትሰምዑ ፡ በአዕዛኒክሙ ፡ ትወድቁ ፡
ውስተ ፡ እሳት ፡ ሕያዋኒክሙ ።

፳ ወይነሥእ ፡ ብእሲ ፡ ንዑሰ ፡ ከልበ ፡ ወየሐፅኖ ፡
ወያዓብዮ ።

፳፩ ወእምድኅረ ፡ ልሒቀ ፡ ይተሉ ፡ ድኅረ ፡ እግ
ዚኡ ፡ ወየሐውር ፡ ውስተ ፡ ገዳም ።



፲፬ አንበሳ ፡ ከጨፈቀ ፡ ዱር ፡ ከጕደጕደ ፡ ምድር
ሸምቆ ፡ ቆይቶ ፡ ላምን ፡ እንዲነጥቅ ፡ እንደዚህም ፡ የእ
ሳት ፡ ላንቃ ፡ የሚቆያችሁ ፡ የእሳት ፡ እራት ፡ እናንተም
የማይጠፋ ፡ የእሳት ፡ ጕድጓድ ፡ አለ ፡ ይቆያችኋል ፡ ይህ
እንዳያገኛችሁ ፡ ተጠበቁ ።

፲፭ እኔ ፡ ግን ፡ ስለናንተ ፡ እተጋለሁ ።
፲፮ በተሐድሶ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ የሰማይና ፡ የም
ድር ፡ ባለቤት ፡ ጌታ ፡ የሚመጣበትን ፡ ሰዓት ፡ ዕለት ፡
አታውቁምና ፡ ሳታውቁ ፡ በፊቴ ፡ እያላችሁ ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ጌጠኛ ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ ለምን ፡ ትደክማላ
ችሁ ።

፲፯ ልባችሁ ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ፡ የጸና ፡ ክሣደ ፡
ልቦናችሁ ፡ የገዘፈ ፡ እናንተ ፡ የእሥራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ
የማይቀረውን ፡ ዕዳ ፡ የምትሞቱበትን ፡ ቀን ፡ አለማሰ
ባችሁ ፡ ስለምንድር ፡ ነው ፡ አለ ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡
ሠርታችሁ ፡ ተዘጋጅታችሁ ፡ ኑሩ ፡ ሲል ፡ ነው ።

፲፰ ከእናንተስ ፡ በወጥመድ ፡ እንዳይያዙ ፡ ተጠ
ብቀው ፡ የሚኖሩ ፡ በሰማይ ፡ የሚበሩ ፡ አዕዋፍ ፡ ይሻላሉ ።

፲፱ እናንተ ፡ ግን ፡ በዓይናችሁ ፡ እናያለን ፡ በጆ
ሮዋችሁ ፡ እንሰማለን ፡ ስትሉ ፡ ነፍሳችሁ ፡ ከሥጋችሁ ፡
ሳይለይ ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ ጕድጓድ ፡ ትወድቃላችሁ ።

፳ ሰው ፡ የውሻ ፡ ቡችላን ፡ ወስዶ ፡ ያሳድገዋል ።

፳፩ ካደገ ፡ በኋላ ፡ ጌታውን ተከትሎ ፡ ወደ
በረሀ ፡ ይሄዳል ።

፴፩ ወይነውም ፡ በህየ ።

፴፪ ወውእቱኒ ፡ ከልብ ፡ ይነብር ፡ ኀበ ፡ እግረ፡ ሊቁ ።

፴፫ ወሶበ ፡ ይሰምዕ ፡ ድምፀ ፡ አራዊት ፡ ይነቁ ፡ ወያንቅሖ ፡ ለእግዚኡ ።

፴፬ ወሶበ ፡ ቀተሎ ፡ ሰብእ ፡ አው ፡ አራዊት ፡ ለሊቁ ፡ ይነብር ፡ ወየዐቅብ ፡ እስከ ፡ ሠሉስ፡ ዕለት ፡ አው፡ ሰዱስ ፡ ዕለተ ፡ ወኢይሁብ ፡ በድኖ ፡ እምቅድመ ፡ ይሙት ፡ በህየ ፡ በእንተ ፡ ሊቁ ።

፴፭ ወእምነ ፡ ከልብ ፡ ኢትኄይሱኑ ፡ አ ፡ ደቂቀ ዕልዋን ፡ ኃደግሙኒ ፡ ኪያየ ፡ ወአምለክሙ ፡ ዘኢኮኑ ፡ አማልክተ ፡ ግብረ ፡ እደ ፡ ሰብእ ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ኢገብሩ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ፤

፴፮ ይክሉኑ ፡ ከማየ ፡ አቅሞቶ ፡ ለሰማይ ፡ ዘእንበለ ፡ ዓምድ ፡ ወለምድርኒ ፡ ላዕለ ፡ ማይ ፡ ሣርሮታ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ።

፴፯ ለመሪር ፡ ረሰይክምዎ ፡ ጥዑመ ፡ ወለጥዑ

ምኒ ፡ መሪረ ፡ ለብርሃን ፡ አምሰልክምዎ ፡ ጽልመተ ፡



፴፩ በበረሀ ፡ ይተኛል ።

፴፪ ያም ፡ ውሻ ፡ ከጌታው ፡ እግር ፡ ሄዶ ፡ ይቀመጣል ።

፴፫ የአራዊት ፡ ድምፅ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እየጮኸ፡ ጌታውን ፡ ያስነሳዋል ።

፴፬ አራዊትም ፡ ሰውም ፡ ቢሆን ፡ ጌታውን ፡ በገደለው ፡ ጊዜ ፡ እስከ ፡ ስድስት ፡ ቀንም ፡ ቢሆን ፡እስከ ሦስት ፡ ቀንም ፡ ቢሆን ፡ ይጠብቀዋል ፡ እንጂ ፡ ውሻው ፡ ሳይሞት ፡ ስለ ፡ ጌታው ፡ ፍቅር ፡ አስከሬኑን ፡ አስቀድሞ ፡ አይሰጥም ።

፴፭ እናንተ ፡ የከዳተኞች ፡ ልጆች ፡ እኔን ፡ ትታችሁ ፡ ሰማይን ፡ ምድርን ፡ ያልፈጠሩ ፡ አምላክነት ፡ የሌላቸውን ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ የሚሆኑ ፡ እኒህን ፡ ጣዖታትን ፡ ማምለካችሁ ፡ አእምሮ ፡ ለብዎ ፡ ከሌለው ፡ ውሻ እናንተ ፡ አትበልጡም ፡ ነበር?

፴፮ እኔን ፡ ማምለክ ፡ ትታችሁ ፡ እነሱንማ ፡ ታመልኩ፡ ዘንድ፡ እንደኔ ፡ ምድርን ፡ በውሃ ፡ ላይ ፡ አጽንቶ፡ መፍጠር ፡ ሰማይንም ፡ ያለ ፡ ምሰሶ ፡ ማቆም ፡ ይቻላቸዋልን ፡ አለ ፡ እግዚአብሔር ።

፴፯ ተድላ ፡ ደስታውን ፡ ኀዘን ፡ መዓልቱን ፡ ሌሊት ብርሃኑን ፡ ጨለማ ፡ ጨለማውን ፡ ብርሃን ፡ መራራውን ጣፋጭ ፡ የሚጣፍጠውን ፡ መራራ ፡ ያደረጋችሁት ፡ ሰውነት ፡ የሚቆራርጥ ፤ መራራውንማ ፡ ከመብላት ፡ ለሰውነት ፡ የሚስማማውን ፡ የላመ ፡ የጣመ ፡ ምግብ ፡ መብላት ፡ አይሻልም ፡ እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጽኑ ፡ ስቃይ ፡

ወለጽልመት ፡ ብርሃን ፡ ለመዓልት ፡ አምሰልክዎሙ ፡
ሌሊተ ፡ ለትፍሥሕት ፡ አምሰልክምዎ ፡ ኀዘነ ።

፷፱ ወእምሊቅ ፡ ኀረይክሙ ፡ ገብረ ።

፸ አኮ ፡ አንትሙ ፡ ዘጸላእክምዎ ፡ አላ ፡ ውእቱ
ጸልዓክሙ ።

፸፩ ወከመ ፡ ልብሰ ፡ ትክቶ ፡ አስቆረርክሙ ።
፸፪ ወመነንክምዎ ፡ ሌሊተ ፤

፸፫ መኑ ፡ ፈጠሮ ፡ ለሌሊት ፡ ዘትገብሩ ፡ ኵሎ
እንዘ ፡ ተሐውሩ ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ግብረ ፡ ኃጢአት ፡ ወአ
ምልኮ ፡ ጣዖት ፡ ወዝሙት ፡ ወቀትል ፡ ወክዒወ ፡ ደም
ወኀበ ፡ ሐራስ ፡ ወትክቶ ፡ ውስተ ፡ ሠሪቅ፡ወትዕግልት ።

፸፬ ወዘንተ ፡ ኵሎ ፡ እንዘ ፡ ትገብሩ ፡ ዓይንየ ፡
ይሬእየክሙ ፡ ወእዝንየ ፡ ይሰምዓክሙ ፡ ወበትዕግሥትየ
አረምም ፡ ለክሙ ።



በሚያመጣ ፡ በጣዖት ፡ ከማመን ፡ሕይወት ፡ መድኃኒት
በሚሆን ፡ በእግዚአብሔር፡ አምኖ ፡ ብርሃን ፡ ለብሶ ፡
ብርሃን ፡ ተጐናጽፎ ፡በባለሟልነት ፡ ገነት ፡ መንግሥተ
ሰማያት ፡ መግባት፡አይሻልም ፡ እስኪ ፡ አስተውሉት ።
፷፱ ሕይወት ፡ መድኃኒት ፡ ከምሆናችሁ ፡ ከኔ፡
ይልቅ ፡ ባርነትን ፡ መረጣችሁ ።
፸ የጠላችሁት ፡ እናንተ ፡ አይደላችሁም ፡ እርሱ
ጠላችሁ ፡ እንጂ ።
፸፩ እንደ ፡ መርገም ፡ ጨርቅ ፡ የተጸየፋችሁ ።
፸፪ በሌሊት ፡ ጨለማ ፡ ለብሳችሁ ፡ ጨለማ ፡
ተጐናጽፋችሁ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ግብረ ፡ ኃጢአት ፡ ልትሠሩ
ትሄዳላችሁ ።
፸፫ ጨለማ ፡ ለብሳችሁ ፡ የኃጢአትን ፡ ስልት
ስልቱን ፡ ሁሉ ፡ ለመሥራት ፡ ጣዖትን ፡ ለማም
ለክ ፡ ለመሰሰን ፡ ሰውን ፡ ለመግደል ፡ የሰውን ፡ ደም ፡
ለማፍሰስ ፡ ደም ፡ ከሆነች ፡ ሴት ፡ ከአራስ ፡ ሴት ፡ ጋራ
በግብር ፡ ለመገናኘት ፡ ለመስረቅ ፡ ለመቀማት ፡ እየሄ
ዳችሁ ፡ የምትሠሩበትን ፡ ሌሊት ፡ የፈጠረ ፡ ማነው ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ አይደለም ።
፸፬ እኔ ፡ ትዕግሥት ፡ የባሕርዬ ፡ ነውና ፡ እየታ
ገሥኋችሁ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ በሕግ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ የተከለከለውን ፡ ማለት ፡ እግዚአብሔር ፡ በደብረ
ሲና ፡ ወርዶ ፡ ለቀደሙ ፡ አባቶቻችን ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡
ጽፎ የሰጣቸውን ፡ ዐሥር ፡ ተብለው ፡ የሚቈጠሩትን ፡

፴፭ ወሶበ ፡ ጸብሐ ፡ ትነሥኡ ፡ ማየ ፡ ወትትሐ
ጸቡ ፡ ከመ ፡ ዘኢገበርክሙ ፡ ኃጢአተ ።

፴፮ ማይኑ ፡ ያነጽሕ ፡ ኃጢአተ ፡ ከመ ፡ እግዚ
አብሔር፡ ወትመጽኡ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከመ፡
ዘኢገበርክሙ ፡ ትትመጠዉ ፡ ሥጋየ ፡ ወደምየ ።

፴፯ ወለክሙሰ ፡ ይመስለክሙ ፡ መብልዓ ፡ ወመ
ስቴ ፡ ኃላፌ ፡ ወትትመጠዉ ፡ በእደ ፡ ካህናትየ ።

፴፰ ወውእተ ፡ ጊዜ ፡ እኤዝዞሙ ፡ ለመላእክትየ
ከመ ፡ ያውፅኡ ፡ እምአፉክሙ ፡ ከመ ፡ ዘትነሥእ ፡ ብእ
ሲት ፡ ሐሪፀ ፡ እምውስተ ፡ ቤታ ፡ ወታነብሮ ፡ ውስተ ፡
መብስል ።

፴፱ ወእምከመ ፡ የብሰ ፡ ታወርዶ ፡ ወታረምጾ
ከመ ፡ ይብስል ።



ሕግና ፡ ትእዛዝ ፡ አፍርሳችሁ ፡ ብዙ ፡ ግብረ ፡ ኃጢአት
ስትሠሩ፡ ዓይኔ ፡ ያያችኋል ፡ ጆሮዬም ፡ ይሰማችኋል ፡
የማላይ ፡ የማልሰማ ፡ አይምሰላችሁ ።

፴፭ ምንም ፡ ኃጢአት ፡ እንዳልሠራችሁ ፡ ሁሉ፡
ሲነጋ ፡ በነጋ ፡ ጊዜ ፡ ውሃ ፡ በመንቀል ፡ ይዛችሁ ፡ ከም
ግላል ፡ ቦታ ፡ ሄዳችሁ ፡ ትታጠባላችሁ ።

፴፮ ሥጋዬን ፡ ደሜን ፡ መቀበል ፡ የሚገባ ፡ ከኃ
ጢአት ፡ ነጽቶ ፡ በቅቶ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ምንም ፡ ኃጢአት
እንዳልሠራችሁ ፡ ሁሉ ፡ በኃጢአት ፡ ጭቃ ፡ ተለስናችሁ
ሥጋዬን ፡ ደሜን ፡ ለመቀበል ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን
የምትመጡ ፡ ውሃ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኃጢአት
ያነጻል?

፴፯ እናንተ ፡ ግን ፡ የሚያልፍ ፡ የሚጠፋ፡ ሥጋዊ
ምድራዊ ፡ ምግብ ፡ መጠጥ ፡ ኢስመስላችሁ ፡ በሚ
ገባ ፡ ቢቀበሉት ፡ ሕይወት ፡ የሚሆነውን ፡ በማይገባ ፡
ቢቀበሉት ፡ ግን ፡ ፍዳ ፡ የሚያመጣውን ፡ ሥጋዬን ፡
ደሜን ፡ ለመቀበል ፡ ወደ ፡ቤተ ክርስቲያን ፡ ትሄዳላችሁ ።

፴፰ ሥጋዬን ፡ ደሜን ፡ በማይረባ ፡ በምትቀበ
ሉበት ፡ ጊዜ ፡ ሴት ፡ ዱቄት ፡ ከጐታ ፡ ውስጥ ፡ አውጥታ
አዘጋጅታ ፡ እንድታበስለው ፡ እኔም ፡ ሥጋዬን ፡ ደሜን
ከአፋችሁ ፡ በእሳት ፡ ጉጠት ፡ አውጥተው ፡ በበረሃ ፡ ለወ
ደቁ ፡ ሕጌን ፡ ለጠበቁ ፡ በአምልኮቴ ፡ ለፀኑ ፡ ባሕታው
ያን ፡ ያቀብሏቸው ፡ ዘንድ ፡ መላእክትን ፡ አዛቸዋለሁ ።

፴፱ ከደረቀ ፡ በኋላ ፡ ፈጽሞ ፡ ይበስል ፡ ዘንድ፡
ከምጣድ ፡ አውርዳ ፡ ከምድጃ ፡ ዳር ፡ እንድታደርገው።

፴ ወተሐውር ፡ ኀበ ፡ ካልእ ፡ ግብረ ፡ ወይመ
ጽእ ፡ ከልብ ፡ ወይነሥእ ፡ ለውእቱ ፡ ኅብስት ፡

፴፩ ወከማሁ ፡ ይነሥኡ ፡ ሥጋየ ፡ ወደምየ ፡ መላ
እክት ፡ እምእፉክሙ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

## በእንተ ፡ ተዘክሮተ ፡ ዕለተ ፡ ሞት ።

፩ ንዑ ፡ ኦ ፡ አኃውየ ፡ ንዘክር ፡ ዕለተ ፡ ሞትነ ፡
ወናንብር ፡ ቅድመ ፡ አዕይንቲነ ።

፪ ወለምንትኑ ፡ ትገይሡ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን
ዘእንበለ ፡ አሚን ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ ዳዊት ፡ ወከንቶ ፡ ገይሣ
ትክሙ ፡ ወያዕቆብኒ ፡ ይቤ ፡ ፍቅረ ፡ ንዋይ ፡ ከልዓተኒ ፡
ንስሐ ፡ በዲበ ፡ ምድር ፡ ሥርዋ ፡ ለኵላ ፡ እኪት ፡ አፍቅሮ
ንዋይ ።

፫ ኦ ፡ አኃውየ ፡ ንዑ ፡ ንመንኖ ፡ ለዝንቱ ፡ ንዋይ ፡
ወአበዊነሂ ፡ መኒኖሙ ፡ ዘንተ ፡ ዓለመ ፡ ኃላፌ ፡ ወረሱ ፡
መንግሥተ ፡ ሰማያት ።

፬ ንስምዖ ፡ ለመድኃኒነ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ምንተ
ይበቊዖ ፡ ለሰብእ ፡ ለእመ ፡ ኵሎ ፡ ዓለመ ፡ ረብሐ ፡ ወነ
ፍሶ ፡ ኃጕለ ።



፴ ሌላውን ፡ ሥራዋን ፡ ለመሥራት ፡ በሄደች ፡
ጊዜ ፡ ውሻ ፡ መጥቶ ፡ ያንን ፡ ዳቦ ፡ ይዞት ፡ ይሄዳል ።

፴፩ እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ መላእክት ፡ ሥጋዬን ፡
ደሜን ፡ ካፋችሁ ፡ አውጥተው ፡ ለበቃ ፡ ሰው ፡ ይሰጡታል።

## ፳፫ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## የማይቀረውን ፡ ዕዳ ፡ የምንሞትበትን ፡ ቀን ስለ ፡ ማሰብ ።

፩ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ የምንሞትበትን ፡ ቀን ፡
በፊታችን ፡ አኑረን ፡ እናስብ ፡ ዘንድ ፡ ኑ፡በፊት፡ ያለ ፡ እን
ዳይጠፋ ፡ በዓይነ ፡ ልቡናችን ፡ እናሳድረው ፡ ሲል ፡ ነው።

፪ ዳዊት ፡ እግዚአብሔር ፡ ካልረዳ ፡ ቤት ፡ እን
ሠራለን ፡ ማለታችሁ ፡ በከንቱ ፡ ነው ፡ እንዳለ ፤ ያዕቆብም፡
የኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ መገኛው ፡ መሠረቱ ፡ ፍቅረ ፡ ንዋይ
ነውና ፡ ገንዘብ ፡ መውደድ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ንስሐ ፡ እን
ዳልገባ ፡ ከለከለኝ ፡ እንዳለ ፡ ሳታምኑ ፡ ሃይማኖት ፡ ሳይ
ኖራችሁ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለምን ፡ ትገሠግሣ
ላችሁ ።

፫ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ አባቶቻችን ፡ ይህን ፡ የሚ
ያልፈውን ፡ ዓለም ፡ ንቀው ፡ አጥቅተው ፡ መንግሥተ ፡
ሰማያትን ፡ ወርሰዋልና ፡ እኛም ፡ እንደነሱ ፡ ይህን ፡ ገን
ዘብ ፡ ንቀን ፡ ለደሀ ፡ ለጠም ፡ አዳሪ ፡ እንስጠው ፡ ገንዘብ፡
መውደድ ፡ ጣዖት ፡ ማምለክ ፡ ነው ፡ ይላል ።

፬ ጌታችን ፡ ሰው ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ በምሉ ፡
በጥቅሉ ፡ ቢገዛ ፡ በነፍሱ ፡ ከተጐዳ ፡ ምን ፡ ይረባዋል ፡
ምን ፡ ይጠቅመዋል ፡ ብሎ ፡ የተናገረውን ፡ እንስማ ።

፰ ወምንተ ፡ እመ ፡ ወሀበ ፡ ቤዛሃ ፡ ለነፍሱ ፡
በዘይድኅን ።

፱ ወይቤ ፡ ፩ ፡ እምቅዱሳን ፡ ወሶበ ፡ ስእነ ፡ አድ
ኅኖ ፡ ባዕድ ፡ ኢንክል ኑ ፡ አድኅኖ ፡ ነፍስነ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

## በእንተ ፡ ምግባራቲነ ፡ ሠናየ ፡ ወእኩየ ፡

፩ ኦ አኃውየ ፡ ፍቁራንየ ፡ ንለቡ ፡ ቃለ ፡ ዝንቱ፡
ድርሳን ፡ ዘይቤ ፡ ሀለዉ ፡ ኀቤነ ፡ ፪ ፡ መላእክት ፡ ፩ ፡ በየ
ማንነ ፡ ወ፩ ፡ በፀጋምነ ፡ እንዘ ፡ ይጽሕፉ ፡ ኵሎ ፡ ዘገ
በርነ ፡ እመሂ ፡ ሠናየ ፡ አው ፡ እኩየ ።

፪ ወመልአከ ፡ ብርሃን ፡ እንዘ ፡ ይጽሕፍ ፡ ኵሎ ፡
ዘገበርነ ፡ ሠናየ ፡ ወመልአከ ፡ ጽልመትኒ ፡ እንዘ ፡ ይጽ
ሕፍ ፡ ዘገበርነ ፡ እኩየ ።

፫ ወሶበ ፡ በጽሐ ፡ ፍልሰትነ ፡ እምዝንቱ ፡ ዓለም፡
ኃላፊ ፡ ወይወስዱ ፡ ቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውእተ ፡
መጽሐፈ ።

፬ ወይመጽኡ ፡ ሚካኤል ፡ ወብርያል ፡ ወይደል
ውዎን ፡ ለውእቶን ፡ መጻሕፍት ።

፭ ወለእመ ፡ ሞዓ ፡ ክርታስ ፡ ዘብርሃን ፡ ይትፌ
ሥሑ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ።



፰ ይድን ፡ ዘንድ ፡ በሚድን ፡ ገንዘብ ፡ የሚድን
በትን ፡ ለነፍሱ ፡ ቤዛ ፡ አድርጎ ፡ በሰጠ ፡ ነበር ፡ ያለውንም።

፱ ከቅዱሳን ፡ ፩ዱ ፡ ሌላውን ፡ ማዳን ፡ ቢሳነን ፡
ሰውነታችንን ፡ ማዳን ፡ ይሳነናል ፡ ያለውንም ፡ እንስማ ።

## ፳፱ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ ክፉና ፡ በጐ ፡ ሥራዎቻችን ።

፩ እግዚአብሔርን ፡ የምትወዱ ፡ እርስ ፡ በርሳ
ችሁ ፡ የምትፋቀሩ ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ በጐም፡ ቢሆን ፡
ክፉም ፡ ቢሆን ፡ የሠራነውን ፡ ሁሉ ፡ እየጻፉ ፡የሚያኖሩ
፩ዱ ፡ በቀኛችን ፡ ፩ዱም ፡ በግራችን ፡ ፪ት ፡ መላእክት ፡
በኛ ፡ ዘንድ ፡ አሉ ፡ ብሎ፡ የተናገረውን ፡ የዚህን ፡ ድርሳን
ቃል ፡ እንወቅ ።

፪ ብርሃን ፡ የተጐናጸፈ ፡ መልአክ ፡ የሠራነውን፡
መልካም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እየጻፈ ፡ የጨለማ ፡ አበጋዝ ፡
ሰይጣንም ፡ የሠራነውን ፡ ክፉ ፡ ሥራችንን ፡ ሁሉ ፡ እየ
ጻፈ ፡ የሚኖሩ ፡ አሉ ።

፫ ኃላፊ ፡ ጠፊ ፡ ከሚሆን ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡በሞት፡
ተለይተን ፡ የምንሄድበት ፡ ቀን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ይህን ፡
መጽሐፍ ፡ ወስደው ፡በእግዚአብሔር ፡ ፊት፡ ያቀርቡታል ።

፬ ብርያል ፡ የሚባል ፡ ሰይጣንና ፡ ሚካኤል ፤
መጥተው ፡ እኒያን ፡ መጻሕፍቶች ፡ ያመዛዝኗቸዋል ።

፭ የበጐ ፡ ሥራ ፡ ሚዛን ፡ የመዘነ ፡ እንደሆነ ፡
አብ ፡ ወልድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።

፮ ወይቤሎ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመልአከ ፡ ብር
ሃን ፡ አምጽኣ ፡ ለንጽሕት ፡ ወብርህት ፡ ነፍስ ፡ በሠናይ፡
ወበናህይ ፡ ወበዕረፍት ፡ ወበሰላም ፡ ዘእንበለ ፡ ደዌ ፤
ወሕማም ፡ እንዘ ፡ ትብላ ናሁ፡ ሞዕኪዮ ፡ ለዓለም ፡ ወአስተ
ኃፈርኪዮ ፡ ለጸላዒኪ ፡ ሰይጣን ።

፯ ወይትፌሥሑ ፡ ሠራዊተ ፡ ሰማያት ፡ እንዘ ፡
ይብሉ፡ ኦ፡ ንጽሕት፡ ወብርህት ፡ ነፍስ ፡ ወፅዕዱት ፡ ከመ፡
ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ፄኖክነ ፡ ወምዕዝክነ ።

፰ ኦ፡ ነፍስ ፡ ብርህት ፡ ከመ ፡ ፀሐይ ፡ ወተቀበልዋ፡
መላእክት ፡ በስብሐት ፡ ወበማዕጠንት፡ ወበመጣዕቅት ፡
ወውስተ ፡ እደዊሆሙ ፡ አክሊላት ፡ ዘወርቅ ፡ ወብሩር ።

፱ ወቦ ፡ ከመ ፡ ቀስተ ፡ ደመና ፡ ዘግቡር ፡ በናር
ዶስ ፡ ቦ ፡ ዘእሳት ፡ ወቦ ፡ ዘመባርቅት ።

፲ ወይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ኃምስ ፡ ሰማይ ፡ክርስቶስ
ወጳራቅሊጦስ ፡ ጻድቃን ፡ ወቅዱሳን ፡ ሰማዕት ፡ ምእመ
ናን ፡ ወማርያም ፡ እሙ ፡ ለእግዚእነ ፡ ወኵሎሙ ፡ ደናግል
ምስሌሃ ፡ ወይብልዋ፡ ሰላም ፡ ለኪ ፡ ኦ ፡ ብርህት ፡ ነፍስ፡
ዘአሥመርኪዮ ፡ ለፈጣሪኪ ፡ በኵሉ ፡ መዋዕለ፡ ሕይወትኪ።

፲፩ ወለመልአኪ ፡ ብርሃንኪ ፡ ዘነበረ ፡ ምስሌኪ ፡
ኢያስተኃፈርኪ ።



፮ እግዚአብሔርም ፡ መልአከ ፡ ብርሃንን ፡ ጠላ
ትሽ ፡ ሰይጣንን ፡ ይህንን ፡ ዓለም ፡ እነሆ፡ድል፡ነሥተሽ፡
አሳፈርሽው ፡ እያልህ ፡ ያለ ፡ ጽኑዕ ፡ ደዌ ፡ መከራ፡በፍቅር፡
በ፩ነት ፡ በዕረፍት ፡ በበገሙ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ጽድልት ፡
ብርሀት ፡ ንጽሕት ፡ ነፍስን ፡ አምጣት ፡ ይለዋል ።

፯ ሠራዊት ፡ ሰማያትንም ፡ ንጽሕት ብርሀት ፡
ጽድልት ፡ ነፍስ ፡ ሆይ ፡ እንደ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ መዓዛሽ ፡
ሽታሽ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው፡ እያሉ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል።

፰ መላእክትም ፡ በእጃቸው ፡ ኅብሩ ፡ የብርና ፡
የወርቅ ፡ ኅብር ፡ የሚመስል ፡ አክሊል ፡ በእጃቸው፡ይዘው ፡
የብርሃን ፡ ደወል ፡ እየመቱ ፡ ጥና ፡ ይዘው ፡ እያጠኑ ፡
በምስጋና ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ የምታበሪ ፡ ነፍስ ፡ ሆይ ፡
እያሉ ፡ ይቀበሏታል ።

፱ ኅብሩ ፡ መባርቅት ፡ የእሳት ፡ ላንቃ ፡ የሚ
መስል ፡ የናርዶስ ፡ አበባ ፡ ኅብር ፡ በሚመስል ፡ ኅብር ፡
እንደተሠራ ፡ ቀስተ ፡ ደመና ፡ የሚመስል ፡ አለ ።

፲ ደናግልን ፡ ሁሉ ፡ አስከትላ ፡ የጌታችን፡ እናት
እመቤታችን ፡ ምእመናን ፡ ሰማዕታት ፡ ንዑዳን ፡ ክቡ
ራን ፡ የሚሆኑ ፡ ጻድቃን ፡ ናዛዚ ፡ ከሣቲ ፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡
ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ወደ ፡ ፫ኛው ፡ ሰማይ ፡ ወርደው ፡
ባለ ፡ ዘመንሽ ፡ ሁሉ ፡ ፈጣሪሽን ፡ ደስ ፡ ያሰኘሺው ፡
ጽድልት ፡ ብርሀት ፡ ነፍስ ፡ ሆይ ፡ ፩ነት ፡ ፍቅር ፡ ይገ
ባሻል ፡ እያሉ ፡ በክብር ፡ ይቀበሏታል ።

፲፩ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ የነበረ ፡ መልአከ ፡ ብርሃንንም ፡
የማይገባ ፡ ሥራ ፡ ሠርተሽ ፡ አላሳፈርሽውምና ።

፲፪ ሃሌ ፡ ሉያ ፡ ለአብ ፡ ስብሐት ፡ ለወልድ ፡ ባርኮት ፤
ለመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ለዘወሀበኪ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ።

፲፫ ወወሀበኪ ፡ መዊአ ፡ ትኪዲ ፡ ርእሶ ፡ ለሰይጣን ፡
ወትቀጥቅጢ ፡ ኃይሎ ፡ ለጸላዒ ፡ ወሠራዊቶ ፡ ሊዘዜወቀ ፡
ለዛቲ ፡ ነፍስ ፡ ወመርሃ ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይት ።

፲፬ ወአብጽሕዋ ፡ ለእንትኩ ፡ ነፍስ ፡ ኀበ ፡ አብ ።

፲፭ ወአልበሳ ፡ አብ ፡ ጸዓዳ ፡ ልብሰ ፡ ዘእምላዕሉ ፡
ተአንመ ፡ ወኃተማ ፡ ገጻ ፡ በእደዊሁ ፡ ቅዱሳት ፡
ወይቤላ ፡ ሑሪ ፡ ባኢ ፡ ውስተ ፡ ዩናሆሙ ፡ ለቅዱሳን ፡
አበው ኪ ።

፲፮ ወይወስድዋ ፡ ውስተ ፡ ገነተ ፡ ትፍሥሕት ።

፲፯ ወይትቀበልዋ ፡ ጻድቃን ፡ ወይብልዋ ፡ ንዒ ፡
ማዕከሌነ ፡ ንጽሕት ፡ ወብርህት ፡ ነፍስ ።



ቅድመ ፡ ዓለም ፡ ለነበረ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማ
፲፪ ለመውረስ ፡ ላበቃሽ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አብ ፡
ያትን ፡ መመስገን ፡ ይገባዋል ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ወላዲ ፡ ተብሎ ፡ መመስገን ፡ ይገባዋል ፡
ወልድም ፡ ተወላዲ ፡ ተብሎ ፡ መመስገን ፡ ይገባዋል ፡
ለእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ሠራዒ ፡ ተብሎ ፡
መመስገን ፡ ይገባዋል ።
ያችን ፡ ነፍስ ፡ በሃይማኖት ፡ አጽንቶ ፡ ምግ
፲፫ ባር ፡ ትሩፋት ፡ አሠርቶ ፡ መንፈሳዊ ፡ ምርኮ ፡ ማርኮ ፡
እየመራ ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ላደረሳት ፡ ከነሠ
ራዊቱ ፡ የጸላዒ ፡ የዲያብሎስን ፡ ኃይሉን ፡ ታደክም ፡
ዘንድ ፡ የሰይጣንንም ፡ ቸብቸቦውን ፡ በሰይፈ ፡ ትሩፋት ፡
ቆርጠሽ ፡ ባሕረ ፡ እሳትን ፡ እየጠቀጠቀች ፡ ትሄድ ፡
ዘንድ ፡ ድል ፡ መንሳትን ፡ ለሰጣት ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይገባዋል ።
፲፬ እንዲህ ፡ እያመሰገኑ ፡ ያችን ፡ ነፍስ ፡ ወደ
አብ ፡ አደረሷት ።
፲፭ አብም ፡ በግብር ፡ አምላካዊ ፡ የተሠራ ፡
ኀብሩ ፡ በረድ ፡ የሚመስል ፡ የብርሃን ፡ መጐናጸፊያ ፡
አጐናጽፎ ፡ ንጹሐት ፡ ክቡራት ፡ በሚሆኑ ፡
እጆቹ ፡ ፊቷን ፡ ባርኮ ፡ ንዑዳን ፡ ክቡራን ፡ አባቶችሽ ፡
የተዋሐዳቸው ፡ አእምሮ ፡ የሚመስጥ ፡ በጐ ፡ መዓዛ ፡
ወዳለበት ፡ ሂደሽ ፡ ግቢ ፡ አላት ።
፲፮ መላእክትም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታዘው ፡
ተድላ ፡ ደስታ ፡ ወዳለበት ፡ ገነት ፡ ወስደው ፡ ያገቧታል ።
፲፯ ጻድቃንም ፡ በማክበር ፡ ተቀብለው ፡ ንጽ
ሕት ፡ ክብርት ፡ ብርህት ፡ ነፍስ ፡ ነይ ፡ በመካከላችን ፡
ተቀመጭ ፡ ይሏታል ።

፲፰ ወየሐትቶ ፡ መልአክ ፡ ብርያል ፡ ለመልአከ ፡ ጽልመት ፡ ወይቤሎ ፡ ኢይቴ ፡ ነበርከ ፡ እምንእሱ ፡ እስከ ፡ መዋዕለ ፡ ርስእናሁ ፡ ወእስከ ፡ ተፍጻሜተ ፡ መዋዕሊሁ ፡ ደመርኩ ፡ ኪያከ ።

፲፱ ወአይቴ ፡ ነበርከ ፡ በሐኬት ፡ ወበቍጥዓ ፡ ለምንት ፡ ኢሞእኮ ።

፳ ወአውሥአ ፡ መልአከ ፡ ጽልመት ፡ ወይቤሎ ፡ ለብርያል ፡ በዝኒ ፡ አመከርክዎ ፡ ወሞአኒ ።

፳፩ በሰሐቅ ፡ ወበዘፈን ፡ በሐሜት ፡ ወበሰላቅ ፡ በትእቢት ፡ ወትዝኅርት ፡ ወለምንት ፡ በዝኒ ፡ ኢያስተኃፈርኮ ።

፳፪ ወይቤሎ ፡ በዝንቱ ፡ ኵሉ ፡ ሰእንክዎ ፡ ወሞአኒ ።

፳፫ በዝሙት ፡ ወበሐዊረ ፡ ብእሲተ ፡ ብእሲ ፡ በቀቲል ፡ ወበአምልኮ ፡ ጣዖት ፡ በንዋም ፡ በዝኒ ፡ ለምንት ፡ ኢሞእኮ ፡ ወኢያስጠምኮ ።

፳፬ ወይቤሎ ፡ በዝኒ ፡ ሞዓኒ ።



፲፰ የክህደት ፡ የኃጢአት ፡ መልክተኛ ፡ ብርያል ፡ የሚባል ፡ ሰይጣንም ፡ የጨለማ ፡ አበጋዝ ፡ ባለሟሉን ፡ ከእናቱ ፡ ማሕፀን ፡ ጀምሮ ፡ ተወልዶ ፡ እስቲያረጅ ፡ ድረስ ፡ መላ ፡ ዘመኑን ፡ እስኪፈጽም ፡ ድረስ ፡ አንተን ፡ አስተህ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ታወርዳቸዋለህ ፡ መስሎኝ ፡ ባልደ ረባ ፡ አድርጌ ፡ ነበር ፡ ወዴት ፡ ነበርክ ፡ ብሎ ፡ ይመረ ምረዋል ።

፲፱ ሥራ ፡ በማስፈታት ፡ በመቆጣት ፡ ድል ፡ አለመንሳትህ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ምን ፡ ሁነህ ፡ ነው ፡ ይለዋል ።

፳ የጨለማ ፡ አበጋዝ ፡ ሰይጣን ፡ አለቃውን ፡ ዲያብሎስን ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ተፈታትኜው ፡ ነበር ፡ ድል ፡ ነሳኝ ፡ እንጂ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

፳፩ በዘፈን ፤ በሳቅ ፤ በስላቅ ፤ በዋዛ ፤ በፈዛዛ ፤ ሰውን ፡ በማማት ፡ በመታበይ ፡ ባካሄድ ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ያላሳፈርከው ፡ ስለምን ፡ ነው ።

፳፪ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ተፈታትኜው ፡ ነበር ፡ ድል ነሳኝ ፡ እንጂ ፡ አለው ።

፳፫ በመሰሰን ፡ ከጐልማሳ ፡ ሚስት ፡ በመሄድ ፡ ነፍስ ፡ በመግደል ፡ ጣዖት ፡ በማምለክ ፡ ዕንቅልፍ ፡ በማ ምጣት ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ በባሕረ ፡ ኃጢአት ፡ ያላሰጠም ኸው ፡ ድል ፡ ያልነሳኸው ፡ ስለምን ፡ ነው ።

፳፬ በዚህም ፡ ሁሉ ፡ ተፈታትኜው ፡ ነበር ፡ ድል ነሣኝ ፡ እንጂ ፡ አለው ።

፳፭ ወተንሥአ ፡ ሶቤሃ ፡ ብርያል ፡ መልአክ ፡
ወጸፍዖ ፡ አፉሁ ፡ ውገጾ ፡ በመጥባሕተ ፡ እሳት ።

፳፮ ወእምብዝኃ ፡ ጽፍዓት ፡ ወድቀ ፡ ዲበ ፡
ምድር ።

፳፯ ወነሥአ ፡ አክሊለ ፡ ዘወህቦ ፡ እምዲበ ፡ ርእሱ
ወሐቀየ ፡ ስነኒሁ ፡ በመዓት ፡ ወበቍጥዓ ።

፳፰ ወይሰብር ፡ ስነኒሁ ፡ ፺ተ ፡ በእመተ ፡ መላ
እክት ።

፳፱ ወአብዝኃ ፡ ቊጥዓ ፡ ወከልአ ፡ አክሊለ ፡ እም
ዲበ ፡ ርእሱ ።

፴ ወይበኪ ፡ አንብዓ ፡ መሪረ ፡ ፴ ፡ ዕለተ ፡ ወ፴፡
ሌሊተ ፡ ወይብል ፡ ወይ ፡ ሊተ ፡ ወአሌ ፡ ሊተ ፡ ሰሐቀ ፡
ኮንኩ ፡ ለኵሉ ፡ እለ ፡ ይጼውዑ ፡ ስሞ ፡ ለኢየሱስ ፡ ክር
ስቶስ ፡ወይመትር ፡ ጕርዔሁ ፡ በጽፍሩ ።

፴፩ ወጽፍረ ፡ እደዊሁ ፡ ፻ ፡ ወ፴ ።

፴፪ ወይረግጾ ፡ ከሣዶ ፡ ወይወስዶ ፡ ውስተ ፡
ማዕምቅቲሃ ፡ ለሲኦል ፡ ወይሬስዮ ፡ መንጸፈ ፡ ደይን ፡
ወይነብር ፡ ዲቤሁ ፡ ከመ ፡ ኢያንሳሕስሕ ፡ ወይከይዶ ፡
በእገሪሁ ።



፳፭ ብርያል ፡ የሚባል ፡ መልአክ ፡ ጽልመትም፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ ተንሥቶ ፡ ፊቱንም ፡ አፉንም ፡ በእሳት ፡ ሾተል
ጸፋው ።

፳፮ መላልሶ ፡ ከመምታቱ ፡ የተነሣ ፡ መከራው ፡
ቢጸናበት በምድር ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡ አለ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ወረደ ፡ ሲል ፡ ነው ።

፳፯ በባለሚልነቱ ፡ ጊዜ ፡ የሰጠውን ፡ የእሳት ፡
አክሊል ፡ በመበሳጨት ፡ በመቆጣት ፡ ጥርሱን ፡ እያጠ
ራጠሰ ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ አውርዶ ፡ ወሰደበት ።

፳፰ በመላእክት ፡ ክንድ ፡ ፺ት ፡ የሚሆን ፡ ጥር
ሱን ፡ ይሰብራል ።

፳፱ ፈጽሞ ፡ ይበሳጫል ፡ ፡ የጨለማ ፡ አክሊሉንም
ከራሱ ፡ ላይ ፡ አውርዶ ፡ ይጥልበታል ።

፴ ጕሮሮውን፡በጥፍሩ፡እየቧጠጠ፡የኢየሱስ፡ክርስ
ቶስን፡ስም፡በምስጋና፡በሚጠሩ፡በምእመናን ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ፡
መዘባበቻ ፡ ለሆንኩ ፡ ለኔ ፡ ወዮልኝ ፡ ወዮታ ፡ አለብኝ ፡
ወዮ ፡ ሊሉልኝ ፡ ይገባል ፡ እያለ ፡ ፴ ፡ መዓልት ፡ ፴ ፡
ሌሊት ፡ መራራ ፡ ዕንባን ፡ እያወረደ ፡ ያለቅሳል ።

፴፩ የእጁ ፡ ጥፍር ፡ መቶ ፡ ዓርባ ፡ ክንድ ፡
ይሆናል ።

፴፪ እንዳይንቀሳቀስ ፡ አንገቱን ፡ በግሩ፡ ተረግጦ፡
በጀርባው ፡ ዐደባባይነት ፡ እየተመላለሰ ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡
ጥልቅ ፡ መከራዋ ፡ ወስዶ ፡ የደይን ፡ ምንጣፍ ፡ ያደርገ
ዋል ፡ አለ ፡ በፍዳ ፡ ላይ ፡ ፍዳ ፡ ያመጣበታል ።

፹፫ ወሶበ ፡ ሞአ ፡ መልአከ ፡ ጽልመት ፡ ይፌንዎ፡ ጰራቅሊጦስ ፡ ለጻዕረ ፡ ሞት ፡ ላዕለ ፡ ይእቲ፡ ነፍስ፡ትትጋር ምት ፡ ወዓላዊት ፡ ወይበ ፡ ዑ ፡ ውስተ ፡ ልባ ፡ ወኢይመትራ ፡ በጊዜሁ ፡ ኦላ ፡ የዓይላ ፡ ወያግዕራ ፡ እስከ ፡ ፫ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ እስከ ፡ ፯ ፡ ዕለት ፡ ወሌሊተ ፡ ወኢያእርፋ ፡ አላ ፡ በእኩይ ፡ ሞት ፡ ወይቀትላ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ ዳዊት ፡ ሞቱ ፡ ለኃጥእ ፡ ጸዋግ ።

፹፬ ወካዕበ ፡ ይቤ ፡ ክቡር ፡ ሞቱ ፡ ለጻድቅ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ።

፹፭ ወይወስድዋ ፡ በዓቢይ ፡ ገዓር ፡ ወበብካይ ፡ እንዘ ፡ ያቴክልዋ ፡ ወይገፍዕዋ ።

፹፮ ወትቤሎሙ ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡ አዕርፉኒ ፡ ንስቲተ ፡

፹፯ ወይብልዋ ፡ አልብኪ ፡ ዕረፍት ፡ በዝየኒ ፡ ወበከሀ ፡ ወይዘብጥዋ ፡ በአብትረ ፡ እሳት ፡ ወይብልዋ ፡ ሩጺ ፡ ወእፍጥኒ ።

፹፰ ወይገፍዕዋ ፡ ከመ ፡ ዘይነድዕዎ ፡ ለላህም ፡ በዕለተ ፡ ጥብሐት ፡ ቅድመ ፡ ንጉሥ ፡ ከማሁ ፡ ይሬስይዋ ፡ ለነፍስ ፡ ኃጥእት ።



ጰራቅሊጦስ ፡ የጨለማ ፡ አበጋዝ ፡ ሰይጣን ፡
፹፫ የኃጥእ ፡ ሰው ፡ ሞት ፡ ጽኑ ፡ ድል ፡ በነሳ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ የኃጥእ ፡ ሰው ፡ ሞት ፡ ጽኑ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረ ፡ አስጨንቆ ፡ አስጠብቦ ፡ በልዩ ፡ ይገድላታል ፡ እንጂ ፡ አያሳርፋትም ፡ ሦስት ፡ መዓልት ፡ ፫ ፡ ሌሊት ፡ ቢሆን ፡ ፯ትም ፡ ቀን ፡ ቢሆንም ፡ ከሥቃይ ፡ ወደ ፡ ሥቃይ ፡ ያዞራታል ፡ ያስጨንቃታል ፡ እንጂ ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ፈጥኖ ፡ አይገድላትም ፡ በልቡናዋ ፡ አድሮ ፡ የሚያስጨንቃት ፡ ጻእረ ፡ ሞትን ፡ ወራዳ ፡ ጉስቋላ ፡ ስደተኛ ፡ ወደምትሆን ፡ ነፍስ ፡ ይልከዋል ።

፹፬ ዳግመኛም ፡ ዳዊት ፡ የጻድቅ ፡ ሰው ፡ ሞት፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የከበረ ፡ የገነነ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረ ፡ እንደዚህ ፡ ሳይሆን ።

፹፭ ለልደት ፡ ለጥምቀት ፡ የሚታረድ ፡ ሰንጋ ፡ እየደበደቡ ፡ ይዘውት ፡ እንዲወስዱት ፡ አጋንንትም ፡ ያችን ፡ ነፍስ ፡ እየገፉ ፡ እያዳፉ ፡ ግንባሯን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ እያታከሉ ፡ በፍጹም ፡ ልቅሶ ፡ በጭንቅ ፡ ይወስዷታል ።

፹፮ ያችም ፡ ነፍስ ፡ ጥቂት ፡ አሳርፉኝ ፡ ትላቸዋለች ።

፹፯ በዚህም ፡ ዓለም ፡ በወዲያም ፡ ዓለም ፡ ቢሆን ፡ ማረፍ ፡ አይገባሽም ፡ ፈጥነሽ ፡ ሂጂ ፡ እያሉ ፡ በእሳት ፡ መንዶ ፡ መንደልቶ ፡ እየደበደቡ ፡ ይዘዋት ፡ ይሄዳሉ ።

፹፰ ላህምን ፡ በሚታረድበት ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ፊት ፡ እየነዱ ፡ ይዘውት ፡ እንዲሄዱ ፡ ይህችን ፡ ኃጥእት ፡ ነፍስንም ፡ እያጋፉ ፡ እያዳፉ ፡ ይዘዋት ፡ ይሄዳሉ ።

፴፱ ወትቤሎሙ ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡ ለእለ ፡ ይነ
ድእዋ ፡ በእንተ ፡ ስሙ ፡ **ለኢየሱስ** ፡ ንስቲተ ፡ አዕርፉኒ
እስመ ፡ አብራክየ፡ ወአባለ ፡ ሥጋየ ፡ ደክመ ፡ እምብዝኃ፡
ሩጸት ፡ ዘእንበለ ፡ ዕረፍት ።

፵ ወይብልዋ ፡ እሙንቱ ፡ መላእክት ፡ ጸዋጋን ፡
ለይእቲ ፡ ነፍስ ፡ አኮኑ ፡ አንቲ ፡ አቅደምኪ ፡ ክሂዶቶ፡
**ለክርስቶስ** ፡ ዘኢይበቍዐኪ ፡ ወኢያድኅኑኪ ፡ አማል
ክተ ፡ ዘተአመንኪ ፡ ወርእሶሙ ፡ ኢይክሉ ፡ አድ
ኅኖ ፡ አመ ፡ ይመጽእ ፡ **እግዚአብሔር** ፡ በግርምት ፡
አውድ ፡ በመባርቅት ፡ ወበነጐድጓድ ፡ ዘእሳት ፡
ወበጸአዕ ፡ ወድልቅልቅ ፡ ሰማያት ፡ ወምድር ፡ ኢይ
ክሉ ፡ ጸዊረ ፡ መዓቶ ።

፵፩ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ጸርሐት ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡
ወትቤ ፡ ወይልየ ፡ እምሐየሰኒ ፡ ሶበ ፡ ኢተፈጠርኩ ፡
እምእትፈጠር ።

፵፪ ወለምንት ፡ ወፃእኩ ፡ እምከርሠ ፡ እምየ ።
፵፫ ወለምንት ፡ ኢኮነኒ ፡ መቃብረ ፡ ማኅፀና ፡
ለእምየ ።

፵፬ ርግምት ፡ ይእቲ ፡ ዕለት ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡
ተወለድኩ ፡ ወእንተ ፡ ይቤሉኒ ፡ ተባዕት ።
፵፭ ኢትትኈለቁ ፤ ውስተ ፡ አዝማን ፤ ወዓ
መታት ።



፴፱ ያችም ፡ ነፍስ፡ ሳያሳርፉ፡እያጣደፉ፡እያዳፉ፡
ይዘዋት ፡ የሚሄዱ ፡ አጋንንትን ፡ ጉልበቴ ፡ መላው ፡
አካሌ ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ ማረፍ ፡ ከመሮጥ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡
ደክሚልና ፡ ስሙ ፡ ሕይወት ፡ መድኃኒት ፡ ስለሆነ ፡
ስለ ፡ **ኢየሱስ** ፡ ብላችሁ ፡ ጥቂት፡ አሳርፉኝ ፡ ትላቸዋለች ።

፵ እኒህም ፡ መላእክት ፡ ይህችን፡ የተፈረደባትን፡
ነፍስ ፡ ሰማይና ፡ ምድር ፡ ገጹ ፡ መዓቱን ፡ መወሰን ፡
የማይቻላቸውን ፡ ባሕርዩ ፡ የእሳት ፡ ላንቃ፡ የሚመስል፡
ነጐድጓድ ፡ መባርቅት ፡ በማነዋወጽ ፡ ብልጭልጭታ ፡
ወደምታስፈራ ፡ ዐደባባይ ፡ **እግዚአብሔር** ፡ በመጣ ፡
ጊዜ ፡ እራሳቸውን ፡ ማዳን ፡ የማይቻላቸው ፡ የማያድኑሽ፡
የማይረቡሽ ፡ የማይጠቅሙሽን ፡ አማልክት ፡ አምነሽ ፡
**ክርስቶስንማ** ፡ አስቀድመሽ ፡ በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ ሳለሽ ፡
አንቺ ፡ ክደሺው ፡ የለም ፡ እነዚያ ፡ ያድኑሽ ፡ እንጂ ፡ ይሏ
ታል ።

፵፩ ያችም ፡ ነፍስ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ በዕለተ ፡ ፍዳ፡
ተፈጥሬ ፡ ገሃነም ፡ ከምወርድ ፡ ጥንቱን ፡ ሳልፈጠር ፡
ብቀር ፡ ይሻለኝ ፡ ነበር ፡ ወዮልኝ ፡ ወዮታ ፡ አለብኝ ፡ ወዮ
ሊሉልኝ ፡ ይገባል ፡ እያለች ፡ ትጮሃለች ።

፵፪ ከናቴ ፡ ማኅፀን ፡ ለምን ፡ ወጣሁ ፡ ተወለድሁ።
፵፫ የናቴ ፡ ማኅፀን ፡ መቃብር ፡ ያልሆነኝ ፡
ለምን ነው ።

፵፬ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተወለደ ፡ የተባልሁበት ፡ ቀን
የተረገመች ፡ ትሁን ።

፵፭ ከዘመን ፡ ዘመን ፡ አትቈጠር ፡ መቈጠርማ ፡
ምነዋ ፡ የመከራውን ፡ ጽናት ፡ መናገር ፡ ነው ፡ እንጂ ።

፵፮ ወአቀምዋ ፡ ለይእቲ ፡ ነፍስ ፡ ቅድመ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በፍርሃት ፡ ወበረዓድ ።

፵፯ ወሐተታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለይእቲ ፡ ነፍስ
ወይቤላ ፡ አንሰ ፡ መዋዕለ ፡ ሠናያተ ፡ ወሀብኩኪ ፡ ወለ
ምንት ፡ ኢያድኃንኪ ፡ ርእሰኪ ፡ መጻሕፍተ ፡ ወካህናተ ፡
ኢወሀብኩኪኑ ፡ ወኢያውረድኩኑ ፡ ኀቤኪ ፡ ዓይነ ፡
ለርእይ ፡ ወእዝነ ፡ ለሰሚዕ ፡ ለምንትኑ፡ኢሰማዕኪዮሙ ።

፵፰ ወንዋየኒ ፡ ከላዕኩኪኑ ፡ በዘትነስሒ ፡ እም
ብዝኃ ፡ አበሳ ፡ ወኃጢአት ፡ ለምንትኑ ፡ ኢያቅደምኪ ፡
ሰንቀኪ ፡ እንዘ ፡ ተሐውሪ ፡ ርኁቀ ፡ ብሔረ ።

፵፱ ወአልቦ ፡ በህየ ፡ ዘይነሥእ ፡ ንዋየ ፡ ካልዑ
እስመ ፡ በዕለተ ፡ ፍዳ ፡ አልቦ ፡ ቤዛ ፡ ወኢይበቍዕ ፡ ንዋይ
ወኢውሉድ ።

፶ እስመ ፡ በዕለተ ፡ ፍዳ ኢይምሕርዎ ፡ ለዘኢ
መሐረ ።

፶፩ አ ፡ ፍቁራንየ ፡ ንዑ ፡ ንስማዕ ፡ ቃሎ ፡ ለመ
ድኃኒነ ፡ ዘይቤ ፡ አቅድሙ ፡ ሰንቀክሙ ፡ እምቅድመ ፡



፵፮ ያችን ፡ ነፍስ ፡ በመፍራት ፡ በመንቀጥቀጥ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ያቆሚታል ።

፵፯ እግዚአብሔርም ፡ እኔማ ፡ ሰፌ ፡ ዘመናት ፡
ረጅም ፡ ወራት ፡ ሰጥቼሽ ፡ አልነበረም ፡ የጠመመውን ፡
የጐደለውን ፡ መልተው ፡ የሚያስተምሩ ፡
አቃንተው ፡ ዕውቀት ፡ የሚሆኑ ፡ መጻሕፍትንስ ፡ አል
መምህራንን ፡ የምትሰሚበት ፡ ጆሮ ፡ የምታዩበት፡ ዓይን
ሰጠሁሽምን ፡ ምክራቸውን ፡ ሰምተሽ ፡ ትምህ
አልፈጠርሁልሽምን ፡ ለምን ፡ ራስሽን ፡ ያላዳንሽ ፡
ርታቸውን ፡ ተቀብለሽ ፡
ብሎ ፡ ያችን ፡ ነፍስ ፡ ይመረምራታል ።

፵፰ ከሄዱ ፡ በኋላ ፡ ወደማይመለሱበት ፡ ወደ ፡
ሩቅ ፡ አገር ፡ ስትሄጂ ፡ ስንቅ ፡ ነፍስ ፡ ምጽዋት ፡ ምግባር
ትሩፋትን ፡ አስቀድመሽ ፡ ያልሠራሽ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው፡
ከጠቃቅኑ ፡ ከታላላቁስ ፡ ኃጢአት ፡ ብዛት ፡ የ ተነሣ ፡
ንስሓ ፡ በምትገቢ ፡ ገንዘብ ፡ ትገቢ ፡ ዘንድ ፡ ንስሓ ፡ የም
ትገቢበትን ፡ ገንዘብ ፡ ከለከልሁሽን ።

፵፱ ፍዳ ፡ በሚቀበሉበት ፡ ቀን ፡ በዕለተ ፡ ምጽ
አት ፡ ልጅም ፡ ሆነ ፡ ገንዘብም ፡ ቢሆን ፡ የሚያድን ፡ የሚ
ረባ ፡ የሚጠቅም ፡ የለምና ፡ የወንድሙን ፡ ገንዘብ ፡
ገንዘብ ፡ የሚያደርግ ፡ አይኑር ።

፶ ፍዳ ፡ በሚቀበሉበት ፡ ቀን ፡ በዕለተ ፡ ምጽአት
ይቅር ፡ ያላለውን ፡ ይቅር ፡ አይሉትምና ፡ ሥላሴ ፡
ይቅር ፡ እንዲሏችሁ ፡ ይቅር ፡ በሉ ።

፶፩ እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ የምትፋቀሩ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ የምትወዱ ፡ ወንድሞቻችን ፡ ሆይ ፡ ከሞታችሁ፡

ትፃው ፡ እምቤትክሙ ፡ እስመ ፡ አልቦ ፡ ዘይሁበክሙ ፡ በህየ ።

፵፪ ወትቤ ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡ አበስኩ ፡ ወኢያእ
መርኩ ፡ ስረይ ፡ ሊተ ፡ እግዚእየ ።

፵፫ ወያወሥአ ፡ እግዚእ ፡ ለይእቲ ፡ ነፍስ ፡ ወይ
ብላ ፡ እምድኅረ ፡ ሞተ ፡ ሰብእ ፡ ይገብእኑ ፡ ወእምድኅረ
ሞተ ፡ ሰብእ ፡ አልቦቱ ፡ ንስሓ ፡ ወርእስኒ ፡ እምድኅረ ፡
ተመትረ ፡ ይክልኑ ፡ ዳግመ ፡ ሰብእ ፡ ተናገሮ ።

፵፬ ወማይኒ ፡ እምድኅረ ፡ ተክዕወ ፡ ይትሐፈስኑ፡
ጽሩየ ፡ እስኩ ፡ ንግሩኒ ፡ አ ፡ ደቂቀ ፡ ዕልዋን ።

፵፭ ወያወሥአ ፡ ሰማያዊ ፡ ለይእቲ ፡ ነፍስ ፡
ወይቤላ ፡ ስምዓ ፡ ፪ ፡ ወ፫ ፡ እሙን ፡ ውእቱ ።

፵፮ አ ፡ ኅርትምት ፡ ነፍስ ፡ መጻሕፍት ፡ ወካህናት
ነበሩ ፡ ምስሌኪ ፡ ለምንት ፡ ኢሰማዕኪዮሙ ፡ መሪረ ፡
ዘአፍቀርኪ ፡ እምነ ፡ ጥዑም ፡ ወእምነ ፡ ፈጣሪኪ ፡ ባዕ



በኋላ ፡ በሄዳችሁበት ፡ ቦታ ፡ ድኅነት ፡ የምታገኙበትን
ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ገንዘብን ፡ የሚሰጣችሁ ፡ የለምና ፡
በሞት ፡ ነፍሳችሁ ፡ ከሥጋችሁ ፡ ሳትለይ ፡ በሕይወት ፡ ሥጋ፡
ሳላችሁ ፡ አስቀድሞ ፡ ስንቀ ፡ ነፍስ ፡ ምግባር ፡ ትሩፋትን፡
ሠርታችሁ ፡ ተዘጋጅታችሁ ፡ ኑሩ ፡ ያለውን ፡ የመድኃ
ኒታችንን ፡ ቃል ፡ እንሰማ ፡ ዘንድ ፡ ኑ ።

፵፪ ያችም ፡ ነፍስ ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ሳላውቅ ፡
በድያለሁና ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፡ ትላለች ።

፵፫ ጌታም ፡ ያችን ፡ ነፍስ ፡ ሰው ፡ አንገቱ ፡ ከተ
ቆረጠ ፡ በኋላ ፡ ሁለተኛ ፡ መናገር ፡ ይቻለዋልን ፡ ከሞተ፡
በኋላስ ፡ ተመልሶ ፡ የሰውነትን ፡ ሥራ ፡ ሊሠራ ፡ ይቻ
ለዋልን ፡ እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡
ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ሠርቶ ፡ መዳን ፡ አይቻለውም ፡ ብሎ፡
ይመልስላታል ።

፵፬ እናንተ ፡ የከሃድያን ፡ ልጆች ፡ ውሃ ፡ ከፈሰሰ፡
በኋላ ፡ ጸርቶ ፡ ይታፈሳል ፡ እስኪ ፡ ንገሩኝ ።

፵፭ ሰማያዊ ፡ ንጉሥ ፡ ጌታም ፡ ያችን ፡ ነፍስ ፡
የ፪ት ፡ የ፫ት ፡ ሰው ፡ ምስክር ፡ የታመነ ፡ የታወቀ ፤ የተረዳ
ነው ፡ ብሎ ፡ ይመልስላታል ።

፵፮ ከ፬ቱ ፡ ባሕርያተ ፡ ሥጋ፡ ከ፭ተኛ ፡ ባሕርያተ
ነፍስ ፡ ፈጥሮ ፡ አዋሕዶ ፡ ልጅነትን ፡ ሰጥቶ ፡ ካከበረሽ ፡
ከፈጠረሽ ፡ ይልቅ ፡ ምን ፡ ምን ፡ ማዳን ፡ የማይቻላቸው
የማያድኑሽ ፡ አምላክነት ፡ የሌላቸው ፡ ጣዖታትን ፡ ማም
ለክን ፡ የወደድሽ ፡ ከመዓር ፡ ከሸንኮር ፡ ከሚጣፍጥ ፡
ከሕገ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጉሮሮ ፡ ቆርጦ ፡ የሚጥል ፡ እሬት

ዳን ፡ አማልክተ ፡ ዘአፍቀርኪ ፡ ወተአመንኪ ፡ ዘአ
ያድኅኑኪ ።

፻፲፯ አንሰ ፡ ኢይሔሱ ፡ ዘወጽአ ፡ እምአፉየ ፡
ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሑሩ ፡ ሰድዋ ፡ ለዛቲ ፡ ነፍስ ፡ ኀበ፡
አቡሃ ፡ ሰይጣን ፡ ዘአፍቀረት ።

፻፲፰ ወትቤ ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡ ወይ ፡ ሌተ ፡ ወአሌ፡
ሊተ ።

፻፲፱ ወሶበ ፡ ወሰድዋ ፡ ሰምዑ ፡ መላእክት ፡ ቃላ
ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ኀዘኑ ፡ ዓቢየ ፡ ኃዘነ ፡ ወከልሉ ፡ አክሊላ
ቲሆሙ ፡ ጻድቃን ፡ ወሰማዕት ፡ ምእመናን ፡ ይበክዩ ፡
አንብዓ ፡ መሪረ ።

፻፳ ወውእተ ፡ ጊዜ ፡ ይትፌሣሕ ፡ ብርያል ፡ ወይ
ስዕሞ ፡ ርእሶ ፡ ለመልአክ ፡ ዘነበረ ፡ ምስሌሃ ፡ ለነፍስ ፤



የወደድሽ ፡ ጐስቋላ ፡ ወራዳ ፡ ነፍስ ፡ ሆይ
ክህደትን ፡ የሚያስታውቁሽ ፡ መምህራን ፡ መጻሕፍት
ይህን ፡ ሁሉ ፡ ምክራቸው ፡ ትምህርታቸውን
ካንች ፡ ጋር ፡ አልነበሩም ፡ ስለምን ፡ ነው ።
አለመቀበልሽ ፡ ስለምን ፡ ነው ።

፻፲፯ እኔ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ እሩቅ ፡ ብእሲ ፡ የተናገር
ሁትን ፡ የማላስቀር ፡ የማላደርገውን ፡ አልናገርምና ፡
ይህችን ፡ ነፍስ ፡ በሕግ ፡ በአምልኮ ፤ ወደ ፡ ወደደችው ፡
ወደ ፡ ግብር ፡ አባቷ ፡ ዲያብሎስ ፡ ውሰዷት ፡ ይላል፡
እግዚአብሔር ።

፻፲፰ መለኮት ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ በፈረደባት ፡ ጊዜ
ያች ፡ ነፍስ ፡ ዕድል ፡ ፈንታዬ ፡ ጽዋ ፡ ተርታዬ ፡ ገሃነመ ፡
እሳት ፡ ለሆን ፡ ለኔ ፡ ወዮልኝ ፡ ወዮታ ፡ አለብኝ ፡ ወዮ ፤
ሊሉልኝ ፡ ይገባል ፡ ትላለች ፡ አይረባትም ፡ አይጠቅማ
ትም ፡ እንጂ ።

፻፲፱ የጨለማ ፡ አበጋዞች ፡ አጋንንት ፡ እጅ ፡
አድርገው ፡ በሐፀ ፡ እሳት ፡ እየነደፉ ፡ በኲናት ፡ እሳት፡
እየወጉ ፡ እያዳፉ ፡ እያጋፉ ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ሲወስዷዋት ፡
ስታለቅስ ፡ ድምጿን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ መላእ
ክት ፡ አክሊላቸውን ፡ ከራሳቸው ፡ ላይ አውርደው ፡
ፈጽመው ፡ ያዝናሉ ፡ ምእመናን ፡ ጻድቃን ፡ ሰማዕታትም፡
መሪር ፡ ዕንባን ፡ እስከ ፡ ማጉረፍ ፡ ደርሰው ፡ ያለቅሳሉ ።

፻፳ ያን ፡ ጊዜም ፡ ብርያል ፡ የተባለ ፡ ዲያብሎስ ፡
ደስ ፡ ብሎት ፡ ደስ ፡ አሰኝቶ ፡ ያችን ፡ ወራዳ ፡ ጐስቋላ ፡
ነፍስን ፡ ተቆራኝቶ ፡ የነበረውን ፡ ሰይጣን ፡ ከፍቅሩ ፡
ጽናት ፡ የተነሣ ፡ ራሱን ፡ ይስመዋል ፡ ታቅፎም ፡ የወ
ርቅ ፡ አክሊል ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይደፋለታል ፤ ስንኳን ፡

ኅርትምት ፡ ወየሐቅፎ ፡ ወይሁቦ ፡ አክሊለ ፡ ዘወርቅ ፡
ወያዓብዮ ፡ እምነ ፡ መላእክቲሁ ፡ ወያነብሮ ፡ በየማኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

## በእንተ ፡ ዜና ፤ ሙታን ።

፩ ኦ ፡ ፍቁራንየ ፡ እንዘ ፡ ንዜኑ ፡ ዜና ፡ ሙታን ፡
ለሊነ ፡ ንከውን ፡ ለዜና ።

፪ ለስብእሰ ፡ ምክንያት ፡ ቦሙ ፡ ወአንትሙሰ ፡
ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ በምንትኑ ፡ እንከ ፡ ታመከንዩ ፡
ዘንተ ፡ ኵሎ ፡ እንዘ ፡ ትሰምዑ ፡ ስምዐ ፡ ዘይቤ ፡ መጽሐፍ ፡
ለነዳያን ፡ ወለርኁባን ፡ ወለምስኪናን ፡ ለጽሙኣን ፡ ወለዕ
ሩቃን ፡ ወለግዩራን ፡ ለእመ ፡ ገበርክሙ ፡ ዘንተ ፡ ኵሎ ፡
ዘእንበለ ፡ ፍቅር ፡ ከንቱ ፡ ውእቱ ።



የወርቅ ፡ አክሊል ፡ የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ ታህል ፡ የናስ ፡
አክሊልም ፡ የለው ፡ ብሎ ፡ ቢኖረው ፡ ይሰጠው ፡ ነበር ፡
ለማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በክህደት ፡ በኃጢአት ፡ ከሚያገ
ለግሉት ፡ መላእክት ፡ ይልቅ ፡ አክብሮ ፡ በቀኙ ፡ ያስቀ
ምጠዋል ፡ አለ ፡ የባለሟልነቱን ፡ ጽናት ፡ መናገር ፡ ነው ።

## ፳፰ኛ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ ሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ነገር ።

፩ እግዚአብሔርን ፡ የምትወዱ ፡ እግዚአብሔር ፡
የሚወዳችሁ ፡ ወንድሞቻችን ፡ ሆይ ፡ እኛ ፡ የሙታን ፡
ነፍስን ፡ ነገር ፡ ስናወጣ ፡ ስናወርድ ፡ እንደ ፡ ኖርን ፡
በአጋንንት ፡ እጅ ፡ ተይዘን ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ በወረድን ፡
ጊዜ ፡ የፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ መዘባበቻ ፡ እንዳንሆን ፡ ምግባር
ትሩፋት ፡ ሠርተን ፡ ለመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ በቅተን ፡
ተዘጋጅተን ፡ እንኑር ፡ ብዬ ፡ እማልዳችኋለሁ ።

፪ እናንት ፡ ካህናት ፡ ዲያቆናት ፡ ለሰዎችስ ፡
ባናውቅ ፡ ባንማር ፡ ኃጢአት ፡ ሠርተን ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡
ፍዳ ፡ ደረሰብን ፡ ብለው ፡ ቢናገሩ ፡ ምክንያት ፡ አላቸው ፡
ይገባቸዋል ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ ለድሆች ፡ ለመጻውተኞች ፡
ለጦም ፡ አዳሪዎች ፡ ለተራቡ ፡ ብታበሉ ፡ ለተጠሙ ፡
ብታጠጡ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ብታደርጉ ፡
ፍቅር ፡ ከሌለ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ያለውን ፡ መጽሐፍ ፤
ስሙ ፡ ሰምታችሁ ፡ ይህን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ፡ በፍቅር ፡
በሃይማኖት ፡ ፍጹማን ፡ ካልሆናችሁ ፡ በምን ፡ ምክን
ያት ፡ ከፍዳ ፡ እናመልጣለን ፤ ብላችሁ ፡ ታመካኛላችሁ ።

፫ ወለእመ ፡ ወሀብከ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ኵሎ
ዘአጥረይከ ፡ ውእቱሂ ፡ ለእመ ፡ አልቦ ፡ ፍቅር ፡ ከንቱ ፡
ውእቱ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ መክብብ ፡ ኵሉ ፡ ከንቱ ፡ ውእቱ
በከመ ፡ ያጠፍዖ ፡ ማይ ፡ ለእሳት ፡ ከማሁ ፡ ያጠ
ፍዖ ፡ ምጽዋት ፡ ለኃጢአት ።

፬ ምሕረት ፡ ወፍቅር ፡ ወሰላም ፡ እኅታ ፡
ለጾም ።

፭ ባዕልሰ ፡ ዘይጾውም ፡ አኮ ፡ በእንተ ፡ **እግዚአ
ብሔር** ፡ አላ ፡ ከመ ፡ ይትዓቀብ ፡ ንዋዩ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡
ጳውሎስ ፡ ዘኒ ፡ ጾመ ፡ **ለእግዚአብሔር** ፡ ጾመ ፡ ወዘኒ ፡
በልዐ ፡ **ለእግዚአብሔር** በልዐ ፡ ወየአኵቶ ፡ **ለእግዚአብሔር** ።

፮ ወኵሎ ፡ ዘገበርክሙ ፡ በአኰቴተ ፡ **እግዚአብ
ሔር** ፡ ግበሩ ፡ አምላከ ፡ ሰላም ፡ ሰላመ ፡ የሀብክሙ ፡ አሜን ።

፯ ወካዕበ ፡ ይቤ ፡ በወንጌል ፡ እመኒ ፡ ዓይንከ ፡
ያስሕተከ ፡ ምላሕ ፡ እምኔከ ፡ እስመ ፡ ይኄይሰከ ፡ ነቋረከ
ትባዕ ፡ ውስተ ፡ ሕይወት ፡ ዘለዓለም ።

፰ ዘይቤ ፡ ዓይንከ ፡ አኮ ፡ ዓይንከ ፡ አላ ፡ ብእሲ
ትከ ፡ ዘኢተሐውር ፡ በትእዛዝከ ፡ ወበሕግከ ፡ ወኢትትሎ
አሠረከ ።



፫ ያገኘኸውን ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲ
ያን ፡ ብትሰጥ ፡ ሰሎሞን ፡ መክብብ ፡ በሚባል ፡ መጽሐፍ
ውሃ ፡ እሳትን ፡ እንዲያጠፋው ፡ ምጽዋትም ፡ ኃጢአትን፡
ያጠፋዋል ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
ፍቅር ፡ ከሌለ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

፬ ምሕረት ፡ ቸርነት ፡ ፩ነት ፡ ፍቅር ፡ ለጾም ፡ ተባ
ባሪ ፡ ናትና ፡ ፍቅርን ፡ ገንዘብ ፡ አድርጉ ።

፭ ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ የጾመም ፡ **ለእግዚአብሔር** ፡
ብሎ ፡ ጾመ ፡ የበላም ፡ **ለእግዚአብሔር** ፡ ብሎ ፡ በላ ፡ **እግ
ዚአብሔርን** ፡ ያመሰግነዋል ። ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡
ባለጸጋ ፡ ግን ፡ መጾሙ ፡ ገንዘቡ ፡ እንዲጠበቅለት ፡ ነው
እንጂ ፡ **እግዚአብሔርን** ፡ ደስ ፡ አሰኛለሁ ፡ ጥቅም ፡ አገ
ኛለሁ ፡ ብሎ ፡ አይደለም ።

፮ የፍቅር ፡ ያ፩ነት ፡ ባለቤት ፡ አምላክ ፡ ፩ነትን፡
ፍቅርን ፡ በውነት ፡ ይስጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ የምትሠሩትን ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ **እግዚአብሔርን** ፡ በማመስገን ፡ በስምም
ነት ፡ ሥሩ ።

፯ ዳግመኛም ፡ በወንጌል ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ሳለህ ፡ ከመላጡ ፡ አካልህ ፡ ፩ዱ ፡ ሳይጐድል ፡ ኑረህ ፡
ኋላ ፡ ገሃነም ፡ ከምትወርድ ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለህ ፡
ከ፪ቱ ፡ ዓይንህ ፡ ፩ዱ ፡ ጠፍቶ ፡ ኑረህ ፡ ኋላ ፡ መንግሥተ
ሰማይ ፡ ብትገባ ፡ ይሻልሃል ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፤
ዓይንህ ፡ ምክንያተ ፡ ስሕተት ፡ ብትሆንብህ ፡ አውጥተህ
ጣላት ።

፰ ዓይንህም ፡ ያለው ፡ በግብር ፡ የማትመስልህ
በሕግህ ፡ በትእዛዝህ ፡ ጸንታ ፡ የማትኖር ፡ ሚስትህ ፡
ናት ፡ እንጅ ፡ ዓይንህ ፡ አይደለም ።

፱ ፍጡን ፡ አግኅሣ ፡ ወአርኅቃ ፡ እምኔከ ፡ እም
ትንበር ፡ ምስለ ፡ ብእሲት ፡ እኪት ፡ ይኄይሰከ ፡ ነቢር ፡
ምስለ ፡ አናብስት ፡ ወአናምርት ፡ እስመ ፡ ኃዘን ፡ ይእቲ
ለልብ ፡ ወዕቅፍተ ፡ ለእግር ።

፲ ወለእመ ፡ ሖርከ ፡ ውስተ ፡ ፍኖተ ፡ ጸብዕ ፡ በህ
የኒ ፡ ለኀዘን ፡ ትሬስየከ ።

፲፩ ወበከመ ፡ ያደክሞሙ ፡ መንገደ ፡ ኆፃ ፡ ለአ
ዕሩግ ፡ ከማሁ ፡ ታደክም ፡ ብእሲት ፡ ነባቢት ፡ ለብእሲ ፡
የዋህ ።

፲፪ ወእመኒ ፡ እግርከ ፡ ታስሕተከ ፡ ምትራ ፡ ወለ
እመኒ ፡ እዴከ ፡ ታስሕተከ ፡ ምትራ ፡ ወግድፋ ።

፲፫ አኮ ፡ እግርከ ፡ ወእዴከ ፡ ወዓይንከ ፡ አላ ፡
ብእሲትከ ፡ ወውሉድከ ፡ ወአግብርቲከ ፡

፲፬ አግኅሦሙ ፡ ወአርኅቆሙ ፡ እምኔከ ፡ በከመ ፡
ይትመላህ ፡ ሰግላ ፡ እምሥርዊ ፡ ከማሁ ፡ ምልሖሙ ፡
እምኔከ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

## በእንተ ፡ ምግባራተ ፡ ካህናት ።

፩ ወአንትሙኒ ፡ ካህናት ፡ አነ ፡ ኀረይኩክሙ ፡
ወሤምኩክሙ ፡ እምነ ፡ መንግሥት ፡ እንተ ፡ ትኄይስ ፡
ወሀብኩክሙ ፡ ወረሰይኩክሙ ፡ ላእካነ ፡ ለቤተ ፡ ክር
ስቲያንየ ፡ እንተ ፡ አጥረይክዋ ፡ በደምየ ፡ ወእተ
ብክዋ ፡ በዕፀ ፡ መስቀልየ ፡ ዕጹብ ፡ ግብር ፡ ዘኢተገብረ ፡
ለመላእክት ፡ ተገብረ ፡ ለካህናት ።



፱ በሕግህ ፡ በሥርዓትህ ፡ ጸንታ ፡ የማትኖር ፡ ሴት
ለእግር ፡ ዕንቅፋት ፡ ለልብም ፡ የሚከፋፍል ፡ ኃዘን ፡
ናትና ፡ ከክፉ ፡ ሴት ፡ ጋር ፡ ከምትኖር ፡ ከአናምርትና ፡
ከአናብስት ፡ ጋር ፡ መኖር ፡ ይሻልሀልና ፡ ካንተ ፡ ለያት ፡
አርቃት ።

፲ ከጠላት ፡ ጋር ፡ ለመዋጋት ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡
ብትሄድ ፡ በዚያም ፡ እንድታዝን ፡ ታደርግሃለች ።

፲፩ አሸዋ ፡ ባለበት ፡ መንገድ ፡ መሄድ ፡ ሽማግ
ሌዎችን ፡ እንዲያደክማቸው ፡ መቀባጠርን ፡ የምታበዛ
ሴትም ፡ ቅን ፡ የዋህ ፡ ሰውን ፡ ታደክመዋለች ።

፲፪ እግርህም ፡ እጅህም ፡ ምክንያተ ፡ ስሕተት ፡
ብትሆን ፡ ቈርጠህ ፡ ጣላት ።

፲፫ እግርህን ፡ እጅህን ፡ ዓይንህን ፡ ቈርጠህ ፡ ጣል
ማለቱ ፡ ሚስትህን ፡ ልጆችህን ፡ ባሮችህን ፡ ማለቱ ፡ ነው ።

፲፬ ሾላ ፡ ከሥሩ ፡ ተነቅሎ ፡ እንዲወድቅ ፡ እንደ
ዚህም ፡ ሁሉ ፡ ካንተ ፡ አርቀህ ፡ ለያቸው ።

## ፳፮ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ስለ ፡ ካህናት ፡ ሥራዎች ።

፩ እናንት ፡ ካህናት ፡ እኔ ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ መርጬ ፡
ሾምኋችሁ ፡ ከመንግሥት ፡ የሚበልጥ ፡ ሥልጣንን ፡
ሰጠኋችሁ ፡ ለመላእክት ፡ ያልተደረገውን ፡ ዕጹብ ፡ ድንቅ ፡
የሚሆን ፡ ሥራ ፡ ለካህናት ፡ ተደረገ ፡ በተሰቀልሁ
በት ፡ መስቀል ፡ የባረኳት ፡ በደሜ ፡ ገንዘብ ፡ ያደረግኋት
ቤት ፡ ክርስቲያኔን ፡ አገልጋዮች ፡ አድርጌያችሁ ፡ ነበር ።

፪ ወወሀብኩክሙ ፡ ሥልጣነ ፡ ትግሥሡ ፡ ሥጋየ፡ ወደምየ ።

፫ ወመላእክት ፡ ሰማይሰ ፡ እለ ፡ ተፈጥሩ ፡ እምነደ ፡ እሳት ፡ ኢይክሉ ፡ ደፈረ ፡ ሥጋየ ፡ ወደምየ ፡ ዘእንበለ ጉጠተ ፡ እሳት ።

፬ ወእምኔሆሙ ፡ ኪያክሙ ፡ አፈቅር ፡ ወቀባዕኩክሙ ፡ በከመ ፡ ቀባዕክዎ ፡ ለዳዊት ፡ ዘይንዕስ ፡ እምአኃዊሁ ፡ ወአንገሥክዎ ፡ ላዕለ ፡ ደቂቀ ፡ እስራኤል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

## በእንተ ፡ ዘኢይደሉ ፡ አንሥኦ ፡ ስእርተ ፡ ርእስ ።

፩ ወአንትሙኒ ፡ ካህናት ፡ ኢታንሥኡ ፡ ስእርተ ፡ ርእስክሙ ፡ ወጽፍረ ፡ እደዊክሙ ፡ ወእገሪክሙ ፡ ከመ ፡ ኢይኅድር ፡ ጸላዒ ፡ ላዕሌክሙ ፡ ከመ ፡ ኢትትዓቀፉ ፡ ዘእልቦ ፡ መዓት ፡ ወቅኑጥዓ ፡ ይመጽእ ፡ ላዕሌክሙ ።

፪ ወሶበ ፡ ትጸላዕ ፡ ምስለ ፡ ቢጽከ ፡ በትረ ፡ ወእብነ ፡ ያመጽእ ፡ ለከ ፡ ከመ ፡ ዘለአኮ ፡ ከመ ፡ ትዝብጥ ፡ ወትውግር ፡ ወከመ ፡ ወጊረከሂ ፡ ኢያስሕትከ ።

፫ ወለእመ ፡ ሞተ ፡ ውእቱ ፡ ዘወገርኮ ፡ ያኅጉል ፡ ነፍስከ ፡ ወይሬስየከ ፡ ለኃጉል ።



፪ ሥጋዬን ፡ ደሜን ፡ የምታከብሩበትን ፡ የምትለውጡበትን ፡ ሥልጣን ፡ ሰጠኋችሁ ።

፫ ከእሳት ፡ የተፈጠሩ ፡ የሰማይ ፡ መላእክት ፡ ስንኳ ፡ በእሳት ፡ ጉጠት ፡ እንጂ ፡ ሥጋዬን ፡ ደሜን ፡ ደፍረው ፡ በእጃቸው ፡ ሊይዙት ፡ አይቻላቸውም ።

፬ ከወንድሞቹ ፡ በዕድሜ ፡ የሚያንስ ፡ ዳዊትን በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ቀብቼ ፡ እንዳነገሥሁት ፡ እናንተንም ፡ ከመላእክት ፡ አብልጬ ፡ ወደድኋችሁ ።

## ፳፱ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## የራስን ፡ ጠጉር ፡ ማሳደግ ፡ ስለማይገባ ።

፩ እናንት ፡ ካህናት ፡ ጸላዒ፡ ዲያብሎስ፡ ሳይቆጣ ሳይበሳጭ ፡ ትሑት ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ መስሎ ፡ መጥቶ ፡ እንዳያድርባችሁና ፡ እግራችሁን ፡ እንዳትሰነካከሉ ፡ የእጃችሁንና ፡ የእግራችሁን ፡ ጥፍር ፡ ቁረጡ ፡ የራሳችሁንም ፡ ጠጉር ፡ ተላጩ ፡ አታሳድጉ ።

፪ ከባልንጀራህ ፡ ጋር ፡ በተጣላህ ፡ ጊዜ ፡ እንደላከኸው ፡ ሁሉ ፡ እንድትመታበት ፡ በትር ፤ ደንጊያ ፡ ያመጣልሃል ፡ ባመጣልህ ፡ ድንጋይ ፡ መትተኸው ፡ እንዳያስትህ ፡ ዕወቅ ።

፫ ያ ፡ የመታኸው ፡ ሰው ፡ ቢሞት ፡ ለጥፋት ፡ ያደርስሃል ፡ ሰውነትህንም ፡ ያጠፋታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፰ ።

### በእንተ ፡ ስዒረ ፡ ሰንበት ፡ ወአክብሮ ፡

፩ አንትሙኒ ፡ ሕዝብ ፡ ወካህናት ፡ ለምንት ፡
ዘኢታከብሩ ፡ ሰንበቶ ፡ ወአይሁድኒ ፡ ያከብሩ ፡
ሰንበቶሙ ።

፪ ወለእመ ፡ ኢያክበርክሙ ፡ ሰንበተ ፡ ክርስ
ስቲያን ፡ እፌኑ ፡ ብክሙ ፡ ረኀበ ፡ ውብድብደ ፡ ውትቃ
ሥፍተ ፡ በበይናቲክሙ ፡ አንበጣ ፡ ወአናኩዓ ፡
በረደ ፡ ወውኅዘ ፡ ወነፋስ ፡ ዓቢየ ፡ ሐሩረ ፡ ወሐ
ማመ ፡ ፈጸንት ፡ ወግብጠ ፡ ነምረ ፡ ወዝዕበ ፡ ወቈናጽለ
ዓቢየ ፡ ዖፈ ፡ ዘይቀልብ ፡ ዕጐሊክሙ ፡ እምነ ፡ ጓጓ ፡
እሞሙ ።

፫ ወለእመ ፡ አክበርክሙ ፡ ሰንበታትየ ፡ እፌኑ፡
ለክሙ ፡ ሳህልየ ፡ ወምሕረትየ ፡ ወእባርክ ፡ ፍሬ ፡ ምድ
ርክሙ ፡ ወአበዝኅ ፡ ኵሎ ፡ ተግባረክሙ ፡ ወትበልዑ፡
ክራ ሜ ፡ እምበረከትየ ፡ ወእምፍሬ ፡ ተግባርየ ፡ ይቤ ፡
እግዚአብሔር ፡ አወርሰክሙ ፡ ምድረ ፡ ሐዳሰ ፡ እንተ ፡
ታውኅዝ ፡ ሐሊበ ፡ ወመዓረ ፡ በከመ ፡ ለአበዊክሙ ፡
በመዋዕለ ፡ ትካት ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

### በእንተ ፡ ሚጠት ፡ ኀበ ፡ ንስሐ ።

፩ ወይእዜኒ ፡ አኃውየ ፡ ንዑ ፡ ንትመየጥ ፡ ኀቤሁ
ረ ንስሐ ፡ ወያድኅነነ ፡ እምኵሉ ፡ ምግባረ ፡ እኩይ ፡ ወየ



## ፳፰ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### ስለሰንበት ፡ ማክበርና ፡ መሻር ።

፩ እናንት ፡ ቀሳውስትና ፡ ሕዝብ ፡ አይሁድ ፡
ስንኳን ፡ በዓላቸውን ፡ ያከብራሉ ፡ በነፍስ ፡ በሥጋ ፡
የምትከብሩባትን ፡ ሰንበትን ፡ አለማክበራችሁ ፡ ስለምን
ነው ።

፪ የክርስቲያን ፡ ዕረፍት ፡ ሰንበትን ፡ ባታከብሩ
ግን ፡ ከእናታቸው ፡ ክንድ ፡ ገላግልቶቻችሁን ፡ ነጥቆ፡
የሚወስድ ፡ ገናና ፡ ታላቅ ፡ ወፍ ፡ ቀበሮ ፡ ጅብም ፡ ነምር
የሆድ ፡ ጓጓታ ፡ የሆድ ፡ ቁርጠት ፡ ፍጹም ፡ ሐሩር ፡ ነፋስ
ጐርፍ ፡ በረድ ፡ ኩብኩባ ፡ አንበጣን ፡ እርስ ፡ በርሳችሁ
መፈጃጀትን ፡ አባር ፡ ቸነፈር ፡ ረሀብን ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡
አመጣባችኋለሁ ።

፫ ቀዳሚትና ፡ እሑድን ፡ ብታከብሩ ፡ ግን ፡ በቀ
ድሞ ፡ ዘመን ፡ ለአባቶቻሁች ፡ ማርና ፡ ወተት ፡ የምታ
ጐርፍ ፡ ምድርን ፡ አወርሳችኋለሁ ፡ አለ ፡ እግዚአብሔር፡
ብሎ ፡ በኦሪት ፡ እንደተነገረ ፡ ዛሬም ፡ ለናንተ ፡ ከፈጠ
ርሁት ፡ ሁሉ ፡ የተገኘውን ፡ ፍሬ ፡ ካበረከትሁት ፡ በረ
ከት ፡ የተገኘውን ፡ የዘንድሮውን ፡ የከረመውን ፡ መከር
ትበላላችሁ ፡ አዝመራችሁን ፡ ሁሉ ፡ አበረክትላችኋ
ለሁ ፡ ይቅርታዬን ፡ ቸርነቴን ፡ አደርግላችኋለሁ ፡ ከም
ድራችሁም ፡ የተገኘውን ፡ ፍሬውን ፡ እባርከዋለሁ ።

## ፳፱ኛ ፡ ምዕራፍ ።

### ወደ ፡ ንስሐ ፡ ስለ ፡ መመለስ ።

፩ አሁንም ፡ ወንድሞቻችን ፡ ከመላእክት ፡ ጋር
አንድ፡ ሁነን ፡ ዕድል ፡ ፈንታችንን ፡ ጽዋ፡ ተርታችንን፡

ሀበነ ፡ ኃይለ ፡ ወመዊዓ ፡ ላዕለ፡ፀርነ ፡ ዲያብሎስ ፡
ወይክፍለነ ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት ፡ ወድርገተ ፡ ምስለ ፡
መላእክት ።

፪ ንፌኑ ፡ ሎቱ ፡ ስብሐተ ፡ ወአኰቴተ ፡ ለአም
ላክነ ፡ ለዘገብረ ፡ ዘንተ ፡ ኵሎ ፡ ከመ፡የሀበነ፡ ዘዓይን ፡
ኢርእየ ፡ ወዕዝን ፡ ኢሰምዓ ፡ ውስተ ፡ ልበ፡ሰብእ፡ ዘኢተ
ኃለየ ፡ ዘአስተዳለወ ፡**እግዚአብሔር** ፡ ለእለ ፡ ያፈቅርዎ፡
በጸሎታ ፡ ወበስእለታ ፡ **ለቅድስት ፡ ወክብርት ፡ ወላዲተ**
**አምላክ ፡ ማርያም ፡ ወዮሐንስ ፡ መጥምቅ ፡ ወጊዮርጊስ፡**
ገባሬ ፡ መንክራት ፡ ዓቢይ ፡ ሰማዕት ፡ ወኵሎሙ ፡ ቅዱ
ሳን ፡ ወሰማዕት ፡ እለ፡እሥመርዎ፡**ለእግዚአብሔር** ፡ በሕ
ይወቶሙ ፡ ይዜኒ ፡ ወዘልፈኒ ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ፡
አሜን ፡ ወአሜን ፡ ለይኩን ፡ ለይኩን ።

፫ ዘጸሐፈ ፡ ወዘአጽሐፈ ፡ ዘንተ ፡ መጽሐፈ ፡
ተስፌዎ ፡ ተስፋ ፡ በመንግሥቱ ፡ ሰማያት ፡ ይሥረይ ፡
ሎቱ ፡ ኃጢአቶ ።

፬ እ ፡ አበውየ ፡ ካህናት ፡ ጸልዩ ፡ ወባርኩ ፡ ላዕ
ሌየ ፡ ከመ ፡**እግዚአብሔር**፡ ይዕቀበነ ፡ እምዕለት ፡ እኪት
ወእምሰዓታተ ፡ መንሱት ፡ በጸሎታ ፡**ለማርያም** ፡ መስተ
ምህርት ፡ ወመተንብልት ፡ ለኵሉ ፡ ፍጥረት ።



መንግሥተ፡ ሰማያት ፡ ያደርግልን ፡ ዘንድ ፡ ጠላታችን
ዲያብሎስን ፡ ድል ፡ የምንነሣበትን ፡ ኃይልን ፡ ሥልጣንን
ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ከክፉ ፡ ሥራ ፡ የተነሣ ፡ ከሚመጣው ፡
ፍዳ ፡ ያድነን ፡ ዘንድ ፡ በንስሐ ፡ ወደሱ ፡ ኑ ፡ እንመለስ።

፱ ይኸውም ፡ እስከ፡ ዕለተ፡ ሞት ከሞት፡ በኋላ ፡
በእውነት፡ ያለ፡ ሐሰት፡ ይሁንልን፡ ይደረግልንና፡ በሕይ
ወተ ፡ ሥጋ ፡ ሳሉ ፡ **እግዚአብሔርን** ፡ በሕግ ፡ በአምልኮ
ደስ ፡ ባሰኙት ፡ ንዑዳን ፡ ክቡራን ፡ በሚሆኑ ፡ ሰማዕታት
ጻድቃን ፡ ሁሉ ፡ ድንቅ ፡ ተአምራት ፡ በሚያደርግ ፡
ገናና ፡ ሰማዕት ፡ በሚሆን ፡ **በጊዮርጊስ** ፡ አማላጅነት ፡
**በመጥምቀ ፡ መለኮት ፡ ዮሐንስም** ፡አማላጅነት ፡ **አም**
**ላክን ፡ በወለደች ፡ ንዕድ ፡ ክብርት ፡ በምትሆን፡በእመ**
**ቤታችን** ፡አማላጅነት ፡ የሰው ፡ ዓይን ፡ ያላየውን ፡ የሰው
ጆሮ ፡ ያልሰማውን ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡ ያልታሰበውን ፡
**እግዚአብሔር** ፡ በሕግ ፡ በአምልኮ ፡ ለሚወዱት ፡ ሰዎች
ያዘጋጀላቸውን፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን፡ ያወርሰን፡ ዘንድ
ይህን ፡ ሁሉ ፡ ላደረገ ፡ ለፈጣሪያችን ፡ ክብር ፡ ምስጋና ፡
እናቅርብ ።

፲ በመንግሥተ፡ ሰማይ ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ አገኛለሁ ፡
ብሎ፡ ተስፋ ፡ በማድረግ ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ፡ የጻፈ ፡ ያጻፈ፡
ኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ይሰረይለታል ።

፲፩ አባቶቼ ፡ ካህናት ፡ ሆይ ፡ ለፍጥረት ፡ ሁሉ ፡
አማልዳ ፡ ምሕረትን ፡ ቸርነትን፡ በምታሰጥ፡ **በእመቤታ**
**ችን** ፡አማላጅነት ፡ **እግዚአብሔር** ፡ ጥፋት ፡ ከታዘዘበት
ሰዓትና ፡ ከክፉ ፡ ቀን ፡ ይጠብቀኝ ፡ ዘንድ ፡ እኔን ፡ ባር
ኩኝ ፡ ለኔም ፡ ጸልዩልኝ ።

፮ አንብቦ ፡ ኢታጽርዑ ፡ በዕለተ ፡ ሰንበት ፡ ከመ ፡ ትርከቡ ፡ አስበ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ።

፯ ለዘጸሐፎ ፡ ወለዘአንበቦ ፡ ወለዘሰምዐ ፡ ቃላቲሁ፡ ለዝንቱ ፡ ጸሎት ፡ ኅቡረ ፡ ይምሐረነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸባኦት ።

፰ በዳግም ፡ ምጽአቱ ፡ አመ ፡ ይነብር ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ያድኅነነ ፡ እመዓቱ ፡ ወየሐውጸነ ፡ በምሕረቱ ፡ በእንተ ፡ ማርያም ፡ ወላዲቱ ፡ ይምሐረነ ፡ ወይሣሃለነ ፡ ለኵልነ ፡ ሕዝበ ፡ ክርስቲያን ፡ እለ ፡ ተጠመቅነ ፡ በጥምቀቱ ። ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ አሜን ።

ከሰአልናከ ፡ በፊት ፡ የሚጸለይ ፡ ከዳዊት ፡ መዝሙርና ፡ ከነቢያት ፡ መዝሙር ።

ሶበ ፡ ጸዋዕክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፬
እግዚአብሔር ፡ ይሬእየኒ ፡ ፳፪
አምላከ ፡ አማልክት ፡ ፵፱
ተሣሃለኒ ፡ እግዚኦ ፡ በከመ ፡ ዕበየ ፡ ሣህልከ ፡ ፶
ለከ ፡ ይደሉ ። ፷፬
እግዚአብሔር ፡ ይባርከነ ፡ ፷፮
ጥቀ ፡ ፍቁር ፡ ፹፫
አመንኩ ፡ በዘነበብኩ ፡ ፻፲፭
ጸሎተ ፡ ሐና ፡ እመ ፡ ሳሙኤል ፡ ነቢይ ፡ ፬
ኅበ ፡ ባረኩ ፡ አናንያ ፡ ወአዛርያ ፡ ወሚሳኤል ፡ ፲
ጸሎተ ፡ እግዝእትነ ፡ ማርያም ፡ ፲፫
ጸሎተ ፡ ስምዖን ፡ ነቢይ ፡ ፲፭



፮ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ዋጋችሁን ፡ ታገኙ፡ ዘንድ ፡ በዕለተ ፡ ሰንበት ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ ማንበብን አታስታጉሉ ።

፯ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ ጽፎ ፡ ያነበበውን ፡ ሲነበብ ፡ ቃሉን ፡ የሰማውን ፡ እኛንም ፡ ከሱ ፡ ጋር ፡ እንኃይለ ፡ ደሱ ፡ ይማረን ።

፰ አቸናፊ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁለተኛ ፡ መጥቶ ፡ በባሕርይ ፡ ክብሩ ፡ በተገለጸ ፡ ጊዜ ፡ ስለእናቱ ፡ ስለ ፡ እመቤታችን ፡ ብሎ ፡ በሱ ፡ ጥምቀት ፡ የተጠመቅን ፡ የክርስቲያን ፡ ወገኖች ፡ እኛንም ፡ በይቅርታው፡ በቸርነቱ፡ ይጎብኘን ፡ ከመዓቱም ፡ ያድነን ፡ ፈጽሞ ፡ ይቅር ፡ ይበለን ፡ ይማረንም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ አሜን ።



በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አሐዱ ፡ አምላክ ፡ አሜን ።

፩ ሰአልናከ ፡ መሐሪ ፡ ሰአልናከ ፡ ፈጣሪ ፡ ሰአልናከ ፡ ከሃሊ ፡ ሰአልናከ ፡ ገባሪ ።

፪ ሰአልናከ ፡ እግዚኦ ፡ ወአስተብቋዕናከ ፡ ዘኢትፈልጥ ፡ ወኢትሌሊ ፡ ወኢትክልእ ፡ ለዘሰአሉከ ፡ በተአምኖ ።

፫ የማንከ ፡ ነቅዐ ፡ ሕይወት ፡ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ፍሥሐ ፡ ወሐሤት ፡ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ጽዋዕ ፡ ወኅብስት የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ በረከት ፡ ወረድኤት ።

፬ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ሣህል ፡ ወምሕረት ፡ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ርኅራኄ ፡ ወትዕግሥት ፡ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ሕግ ፡ ወሥርዓት ።

፭ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ምግባር ፡ ወሃይማኖት ፡ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ጾም ፡ ወጸሎት ፡ የማንከ ፡ ፈልፈለ ፡ ንስሐ ፡ ወሥርየት ።

፮ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ሰማያውያን ፡ ወምድራውያን ፡ አሜን ፤ (ሠለስተ ፡ ጊዜያተ ፡ በል ፡)

አንድ ፡ አምላክ ፡ በሚሆን ፡ በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም ፡ በእውነት ፡ እናምናለን ።

፩ አቤቱ ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፡ አንተን ፡ እንለምናለን ፡ ከሂሎት ፡ የአንተ ፡ ብቻ ፡ የሚሆን ፡ አንተን ፡ እንማልዳለን ፡ አንተን ፡ እንማፀናለን ።

፪ አቤቱ ፡ በፍጹም ፡ እምነት ፡ ለለመኑህ ፡ ሁሉ ያለመከልከል ፡ የልመናቸውን ፡ ዋጋ ፡ በእኩል ፡ የምትሰጣቸው ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፡ አንተን ፡ እንማልዳለን ።

፫ አቤቱ ፡ እደ ፡ የማንህ ፡ የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ነው ፡ እደ ፡ መዝራዕትህ ፡ የደስታ ፡ መፍለቂያ ፡ ነው ፡ እደ ፡ ሥልጣንህ ፡ ኅብስተ ፡ ሕይወት ፡ ጽዋ ፡ መድኃኒት ፡ ነው ፡ እደ ቸርነትህ ፡ የረድኤት ፡ የበረከት ፡ መፍሰሻ ነው ።

፬ አቤቱ ፡ እደ ፡ ሥልጣንህ ፡ የይቅርታና ፡ የምሕረት ፡ መገኛ ፡ ነው ፤ እደ ፡ ትዕግሥትህ ፤ የርኅራኄና ፡ የቸርነት ፡ መፍለቂያ ፡ ነው ። እደ ፡ ኵርናዕህ ፡ የሕግና ፡ የሥርዓት ፡ መዝገብ ፡ ነው ።

፭ አቤቱ ፡ እደ ፡ ሲድነኖትህ ፡ የምግባር ፡ የሃይማኖት ፡ መሠረት ፡ ነው ፡ እደ ፡ እዘዝህ ፡ የንስሐ ፡ የሥርየተ ኃጢአት ፡ ጐዳና ፡ ነው ።

፮ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በሰማያውያን ፡ መላእክት ፡ በምድራውያን ፡ ጻድቃን ፡ ሰማዕታት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ። (ይህን ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ጸልይ ፡)

፯ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ መላእክት ፡ ትጉሃን ፡ አሜን ።

፰ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ አርባዕቱ ፡ እንስሳ ፡ ጾዋርያነ ፡ መንበር ፡ ዘብርሃን ፡ አሜን ።

፱ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ዕሥራ ፡ ወአርባዕቱ ፡ ካህናት ፡ ሰማይ ፡ ኅሩያን ፡ አሜን ።

፲ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ሚካኤል ፡ ወገብርኤል ፡ አሜን ።

፲፩ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ሱራፌል ፡ ወኪሩቤል ፡ አሜን ።

፲፪ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ሩፋኤል ፡ ወዑራኤል ፡ አሜን ።

፲፫ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ሳቁኤል ፡ ወፋኑኤል ፡ አሜን ።

፲፬ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ራሙኤል ፡ ወሱርያል ፡ አሜን ።

፲፭ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ አፍኒን ፡ ወሰዳክያል ፡ አሜን ።

፲፮ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ፺ወ፱ቱ ፡ ነገደ ፡ መላእክት ፡ ሰባሕያን ፡ አሜን ።



፯ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ትጉሃን ፡ በሚሆኑ ፡ መላእክት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፰ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ የብርሃን ዙፋን ፡ በተሸከሙ ፡ አርባዕቱ ፡ እንስሳ ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፱ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በተመረጡ ፡ በሃያ ፡ አራቱ ፡ ካህናተ ፡ ሰማይ ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በሚካኤልና ፡ በገብርኤል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፩ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በሱራፌልና ፡ በኪሩቤል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፪ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በሩፋኤልና ፡ በዑራኤል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፫ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በሳቁኤልና፡ በፋኑኤል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፬ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በራሙኤልና ፡ በሱርያል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፭ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በአፍኒና ፡ በሰዳክያል፡ በረከት ፡ ባርከን ፡አሜን ።

፲፮ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ምስጋና ፡ የዘውትር ፡ ተግባራቸው ፡ በሆነ ፡ ዘጠና ፡ ዘጠኙ ፡ ነገደ ፡ መላእክት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፯ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ፲ቱወ፮ቱ ፡ ነቢያት ፡ ቅዱሳን ፡ አሜን ።

፲፰ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ፲ወ፪ቱ ፡ ሐዋርያት ፡ ሰባክያነ ፡ ወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ አሜን ።

፲፱ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ፸ወ፪ቱ ፡ አርድእት ፡ ላእካን ፡ አሜን ።

፳ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ፭፻ ፡ ቢጽ ፡ አሠረ ፡ ትምህርት ፡ ተላውያን ፡ አሜን ።

፳፩ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ቅዱሳን ፡ ሰማዕታት ፡ መዋዕያን ፡ አሜን ።

፳፪ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ጻድቃን ፡ ቡሩካን ፡ አሜን ።

፳፫ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ ደናግል ፡ ንጹሓን ፡ አሜን ።

፳፬ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከተ ፡ መነኮሳት ፡ ፍጹማን ፡ አሜን ።



፲፯ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ክቡራን ፡ በሚሆኑ ፡ በዐሥራ ፡ አምስቱ ፡ ነቢያት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፰ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ወንጌልን ፡ ባስተማሩ ፡ በዐሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ሐዋርያት ፡ በረከት ባርከን ፡ አሜን ።

፲፱ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ላዕካነ ወንጌል ፡ በሆኑ ፡ ሰባ ፡ ሁለቱ ፡ አርድእት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ትምህርተ ፡ ወንጌልን ፡ በተከተሉ ፡ በአምስት ፡ መቶ ፡ ባልንጀሮች ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፩ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ጽንዐ መከራን ፡ በአቸናፊነት ፡ በተወጡ ፡ ሰማዕታት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፪ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ፍትወታት ፡ ኃጣውእን ፡ ድል ፡ በነሡ ፡ ቡሩካን ፡ ጻድቃን ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፫ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በንጹሓን ፡ ደናግል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፬ አቤቱ ፡ አምላካችን፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በበቂ ፡ ፍጹማን ፡ በሆኑ ፡ መነኮሳት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፭ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከቱ ፡ ፲ወ፬፼ ፡ ወ፵፬ ፡ ምእት ፡ ሕፃናት ፡ ኅሩያን ፡ አሜን ።

፳፮ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከቱ ፡ ፫፻፲ወ፰ ፡ ርቱዓነ ፡ ሃይማኖት ፡ አሜን ።

፳፯ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከቱ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ወኤጲስ ፡ ቆጶሳት ፡ ቡሩካን ፡ አሜን ።

፳፰ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከቱ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ ልኡካን ፡ አሜን ።

፳፱ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከቱ ፡ ሰንበታት ፡ ክልኤሆን ፡ አሜን ።

፴ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከታ ፡ ለቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አሜን ።

፴፩ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከቱ ፡ ፬ቱ ፡ ወንጌላውያን ፡ መምህራነ ፡ ቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አሜን ።

፴፪ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ በበረከታ ፡ ለእግዚእትነ ፡ ማርያም ፡ ቅድስት ፡ ድንግል ፡ በ፪ኤ ፡ ወላዲተ ፡ አምላክ ፡ ዘበአማን ፡ አሜን ።



፳፭ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ምርጥ ፡ ሕፃናት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፮ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ሃይማኖታቸው ፡ የቀና ፡ በሦስት ፡ መቶ ፡ አሥራ ፡ ስምንቱ ፡ ሊቃውንት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፯ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ቡሩካን ፡ በሚሆኑ ፡ በሊቃነ ፡ ጳጳሳትና ፡ ኤጲስ ፡ ቆጶሳት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፰ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ አገልጋዮችህ ፡ በሚሆኑ ፡ ቀሳውስትና ፡ ዲያቆናት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፱ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በሁለቱ ፡ ሰንበታት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፴ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ በቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፴፩ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ የቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መሪዎቿ ፡ በሚሆኑ ፡ በአራቱ ፡ ወንጌላውያን ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፴፪ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ያለመለወጥ ፡ አምላክን ፡ የወለደች ፡ በድንጋሌ ፡ ሥጋ ፡ በድንጋሌ ፡ ነፍስ ፡ የጸናች ፡ በክብርት ፡ እመቤታችን ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፴፫ ባርከነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ፡ ወሀቤ ፡ ጸጋ ፡
ወሀቤ ፡ ብርሃን ፡ ከመ ፡ ታቁመነ ፡ በየማንከ ፡ ምስለ ፡
አባግዒከ ፡ ቡሩካን ፡ አሜን ።

፴፬ ጻድቅ ፡ ወቅዱስ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወልደ
እግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ወወልደ ፡ ማርያም ፡ ሥግው ፡
ፈኑ ፡ ለነ ፡ እግዚኦ ፡ ኢዴከ ፡ ጽንዕት ፡ ወመዝራዕትከ ፡
ልዕልተ ፡ ዲበ ፡ ዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ንብላዕ ፡ ወንስተይ ፡
አግብርቲከ ፡ ወአዕማቲከ ፡ ርኁባን ፡ ወጽሙዓን ፡ ዘኢያረ
ስዓነ ፡ ስብሓቲከ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡
አሜን ።

፴፭ ኦ ፡ እግዚኦ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡
ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ፍትወተ ፡ ዝሙት ፡ ዘኢያመጽእ ፡
ወንዋመ ፡ ዘኢያበዝኅ ፡ ወጸሎተ ፡ ዘኢያጸርዕ ፡ አሜን ።

፴፮ ኦ ፡ እግዚኦ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡
ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ቂመ ፡ ወበቀለ ፡ ዘያርኅቅ ፡ ሐኬተ ፡
ወጽልዓ ፡ ዘኢያመጽእ ፡ አሜን ።

፴፯ ኦ ፡ እግዚኦ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለ
ዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ዘኢያመጽእ ፡ ንዴተ ፡ ወዘያረስእ ፡ ሁከተ
አሜን ።



፴፫ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ጸጋን
የምትሰጥ ፡ ብርሃንን ፡ የምታጎናጽፍ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡
ከወዳጆችህ ፡ ጋራ ፡ በቀኝህ ፡ ታቆመን ፡ ዘንድ ፡ ባር
ከን ፡ አሜን ።

፴፬ አቤቱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ የባሕር ፡
ልጁ ፡ ከድንግል ፡ ማርያም ፡ ከሥጋዋ ፡ ሥጋ ፡ ከነፍሷ ፡
ነፍስ ፡ ነስተህ ፡ የተወለድህ ፡ እውነተኛ ፡ አምላክ፡ኢየሱስ
ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ከገቢረ ፡ ሠናይ ፡ የተራብን ፡ ከገ
ቢረ ፡ ጽድቅ ፡ የተጠማን ፡ እኛ ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ አገል
ጋዮችህ ፡ ምስጋናህን ፡ በማያዘነጋ፡ ገንዘብ ፡ ለዘለዓለሙ ፡
ከዚህ ፡ ኅብስት ፡ በልተን ፡ እንጠግብ ፡ ዘንድ ፡ ከዚህም ፡
ጽዋ ፡ ጠጥተን ፡ እንረካ ፡ ዘንድ ፡ ንዕድ ፡ ክብርት ፡ የምት
ሆን ፡ መለኮታዊት ፡ እጅህን ፡ ልዑል ፡ ክንድህን ፡ ልከህ
ልን ፡ በዚህ ፡ ኅብስትና ፡ በዚህ ፡ ጽዋ ፡ ላይ ፡ በረከትህን ፡
አሳድር ፡ አሜን ።

፴፭ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡
ከፈቃደ ፡ ሥጋ ፡ የሚያነፃ ፡ ዕንቅልፍ ፡የማያበዛ ፡ ጸሎ
ትን ፡ የማያስተጓጉል ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፴፮ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ጥላ
ቻና ፡ ክፋትን ፡ የማያሳስብ ፡ በቀልን ፡ የሚያርቅ ፡ አድር
ገው ፡ አሜን ።

፴፯ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ችግ
ርን ፡ የማያመጣ ፡ ሁከትን ፡ የሚያስወግድ ፡ አድርገው ፡
አሜን ።

፴፰ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ዘያሴስል ፡ መዓት ፡ ወዘይጼጉ ፡ ትዕግሥት ፡ አሜን ።

፴፱ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ለአፍ ፡ ዘኢይመርር ፡ ወለጉርዔ ፡ ዘኢየኀንቅ ፡ ወለከርሥ ፡ ዘኢያደዊ ፡ ዘይሁብ ፡ ፈውሰ ፡ ወይስእር ደዌ ፡ አሜን ።

፵ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ዘያስተፌሥሕ ፡ ኅዙናነ ፡ ወይናዝዝ ፡ ትኩዛነ ፡ አሜን ።

፵፩ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ዘይሔድስ ፡ ሥጋነ ፡ ትሑተ ፡ ወዘይስእር ርኩሳነ ፡ መናፍስት ፡ አሜን ።

፵፪ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ስሱዓ ፡ ልብ፡ዘያረግዕ፡ ወነውረ ፡ ኀሊና ዘያጠፍእ ፡ አሜን ።

፵፫ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ዘይፌውስ ፡ ሕሙመ ፡ ወዘያጸንዕ ፡ ድኩመ አሜን ።

፵፬ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ዘያርኅቅ ፡ መርገመ ፡ ወዘይመጽእ ፡ ሰላመ አሜን ።

፵፭ አ ፡ እግዚአ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ዘኢያኄሊ ፡ እኩየ፡ በመዓልት ፡ ወበሌሊት፡



፴፰ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህን ፡ ጽዋ ፡ ቁጣን አርቆ ፡ ትዕግሥትን ፡ የሚያሰጥ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፴፱ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ለአፍ ፡ የማይመር ፡ ጉሮሮ ፡ የማያሳንቅ ፡ ሆድ ፡ የማያሳምም ፡ ደዌን ፡ አጥፍቶ ፡ ፈውስ ፡ የሚያሰጥ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ያዘኑትን ፡ የሚያስደስት ፡ የተከዙትን ፡ የሚያረጋጋ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፩ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ በኃጢአት ፡ የተዳደፈውን ፡ ሥጋችንን ፡ የሚያድስ ፡ ርኩሳን ፡ መናፍስትን ፡ የሚሸር ፡ የሚሸረሽር ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፪ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ የልቡና ፡ ስስት ፡ ያለበትን ፡ የሚያራራ ፡ የኀሊናንም ፡ ነውር የሚያጠፋ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፫ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ሕሙም ፡ የሚፈውስ ፡ ደካማውን ፡ የሚያጸና ፡ አድርገው አሜን ።

፵፬ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ መርገምን ፡ የሚያጠፋ ፡ ሰላምን ፡ የሚያመጣ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፭ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ በመዓልትና ፡ በሌሊት ፡ በየሰዓቱም ፡ ሁሉ ፡ ክፉ ፡ የማያስብ፡

ወበኵሉ ፡ ሰዓት ፡ ወጽሩዓ ፡ ዘያተግህ ፡ በጊዜ ፡ ጸሎት ፡ አሜን ።

፵፮ እ ፡ እግዚኦ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ፈልፈለ ፡ ጥበብ ፡ ወአእምሮ ፡ ፈልፈለ ፡ ስብሐት ፡ ወዘምሮ ፡ ፈልፈለ ፡ ሰላም ፡ ወተፋቅሮ ፡ አሜን ።

፵፯ እ ፡ እግዚኦ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ለዘይጸብዕ ፡ ነፍሰነ ፡ ወሥጋነ ፡ ዘይትዋቀስ ፡ ምስሌሁ ፡ በቅድሜከ ፡ ወዘይመውዖ ፡ እስመ ፡ አንተ ውእቱ ፡ ቀዳማዊ ፡ ወደኃራዊ ፡ አልፋ ፡ ወዖ ።

፵፰ እ ፡ እግዚኦ ፡ ረስዮ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወለዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ ለመስተሥርየ ፡ ኵሉ ፡ ኃጢአት ፡ ወለእመቦ ፡ ዘተገብረ ፡ ውስቴቱ ፡ ኅምዝ ፡ ወሥራይ ፡ ይሠዓር ፡ ወይዘርዘር ፡ በስምከ ፡ ቅዱስ ፡ አሜን ።

፵፱ እ ፡ እግዚኦ ፡ ይኩነነ ፡ ዝንቱ ፡ ኅብስት ፡ ወዝንቱ ፡ ጽዋዕ ፡ መብልዓ ፡ ጽድቅ ፡ ዘበአማን ፡ ወስቴ ፡ ሕይወት ፡ ዘበአማን ፡ እስከ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ አሜን ።

፶ ባርክ ፡ ለነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ ዘንተ ፡ ኅብስተ ፡ ወዘንተ ፡ ጽዋዓ ፡ አሜን ።

፶፩ ቀድስ ፡ ለነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ ዘንተ ፡ ኅብስተ ፡ ወዘንተ ፡ ጽዋዓ ፡ አሜን ።



በጸሎትም ፡ ጊዜ ፡ ሰነፍን ፡ ለጸሎት ፡ የሚያተጋ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፮ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ የዕውቀትና ፡ የጥበብ ፡ መፍለቂያ ፡ ምንጭ ፡ የዝማሬና ፡ የምስጋና ፡ መፍሰሻ ፡ ወንዝ ፤ የፍቅርና ፡ የሰላም ፡ መገናኛ ወደብ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፯ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ የነፍስና ፡ የሥጋችን ፡ ጠላት ፡ ዲያብሎስን ፡ በፊትህ ፡ ተከራክሮ ፡ ድል ፡ የሚነሣ ፡ አድርገው ፡ አንተ ፡ ቀድሞ ፡ የነበርክ ፡ ዛሬም ፡ ያለህ ፡ ለዘለዓለሙም ፡ የምትኖር ፡ አልፋ ፡ ወዖ ፡ የምትባል ፡ አምላክ ፡ ነህና ።

፵፰ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ የኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ማስተሥረያ ፡ አድርገው ፡ አቤቱ ፡ መድኃኒት ፡ ሥራይ ፡ መርዝ ፡ በውስጡ ፡ ቢጨመርበት ፡ እንኳ በቅዱስ ፡ ስምህ ፡ ሽረህ ፡ አብርሰህ ፤ ዘርዝረህ ፡ አጥፋው ፡ አሜን ።

፵፱ አቤቱ ፡ ይህ ፡ ኅብስት ፡ የእውነት ፡ የጽድቅ ፡ መብል ፡ ይህም ፡ ጽዋ ፡ የሕይወት ፡ መጠጥ ፡ ይሁነን ፡ በእውነት ፡ ለዘለዓለሙ ፡ አሜን ።

፶ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ይህን ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ባርከህ ፡ ስጠን ፡ አሜን ።

፶፩ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ባርከህ ፡ አክብረህ ፡ ስጠን ፡ አሜን ።

፶፪ አንጽሕ ፡ ለነ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ፡ዘንተ ፡ ኅብስተ ፡ ወዘንተ ፡ ጽዋዓ ፡ አሜን ።

[illegible]

፶፬ አሥምር ፡ ለነ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ ዘንተ ፡ ኅብስተ ፡ ወዘንተ ፡ ጽዋዓ ፡ አሜን ፡ ወንጼውዕ ፡ ስመከ ፡ ኅቡረ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ወበኵሉ ፡ ሰዓት ፡ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ዘጸውዓ ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይድኅን ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም አሜን ።

አቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ወጸሎተ ፡ ሃይማኖት ፡ በል ።



፶፪ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ንጹሕ ፡ አድርገህ፡ስጠን፡አሜን።

[illegible]

ኅብስት ፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ [illegible] አሜን ።

፶፬ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ይህን ፡ ኅብስት፡ ይህንም ፡ ጽዋ ፡ በፍጹም ፡ ክብር ፡ አክብረህ ፡ አስምረህ ፡ ትሰጠን ፡ ዘንድ ፡ በአንድነት ፡ ስምህን ፡ እንጠ ራለን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ የጠራ ፡ ሁሉ ፡ ይድናልና ለዘለዓለሙ ፡ አሜን ።

አቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ጸሎተ ፡ ሃይማኖትን ፡ በል ።



አክሊለ ፡ ሦክ ፡ ወኵርዓተ ፡ ርእሱ ፡ ለእግዚእነ ።

# ማ ው ጫ

| ተራ ቍ/ | አርእስት | ገጽ |
|---|---|---|
| ፳፮ | በእንተ ፡ ኅርየተ ፡ መሥዋዕት ፡ | ፶፰ |
| ፳፯ | በእንተ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ | ፷፩ |
| ፳፰ | በእንተ ፡ ኅርየተ ፡ ካህናት ፡ ወዲያቆናት ፡ | ፷፫ |
| ፳፱ | በእንተ ፡ ኃዲገ ፡ አበሳ ፡ | ፷፯ |
| ፴ | በእንተ ፡ አውሥእ ፡ አቡነ ፡ ዘበሰማያት | ፸፪ |
| ፴፩ | በእንተ ፡ ውሂበ ፡ ምጽዋት ፡ | ፸፬ |
| ፴፪ | በእንተ ፡ ገይሠ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ | ፸፭ |
| ፴፫ | በእንተ ፡ ተውኔት ፡ | ፹ |
| ፴፬ | በእንተ ፡ ሕዝብ ፡ ቀዊመ ፡ ቅድመ ፡ ንጉሥ ፡ | ፹፪ |
| ፴፭ | በእንተ ፡ መሃይምናን ፡ እለ ፡ ዐቀቡ ፡ ሕጎ ፡ | ፹፬ |
| ፴፮ | በእንተ ፡ ሰሚዐ ፡ ቃሉ ፡ ለመድኃኒነ ፡ | ፹፯ |
| ፴፯ | በእንተ ፡ እለ ፡ ኖሙ ፡ ዘቢጠ ፡ እንግድዓ ፡ | ፺፪ |
| ፴፰ | በእንተ ፡ ፍቅረ ፡ ቢጽ ፡ | ፻፪ |
| ፴፱ | በእንተ ፡ ጸሊዓ ፡ እግዚአብሔር ፡ | ፻፯ |
| ፵ | በእንተ ፡ ርደተ ፡ መና ፡ | ፻፲ |
| ፵፩ | በእንተ ፡ ሞተ ፡ እግዚእነ ፡ | ፻፲፪ |
| ፵፪ | በእንተ ፡ ተዘክሮተ ፡ ዕለተ ፡ ሞት ፡ | ፻፳፩ |
| ፵፫ | በእንተ ፡ ምግባራቲነ ፡ ሠናየ ፡ ወእኩየ ፡ | ፻፳፬ |
| ፵፬ | በእንተ ፡ ዜና ፡ ሙታን ፡ | ፻፴፬ |
| ፵፭ | በእንተ ፡ ምግባራተ ፡ ካህናት ፡ | ፻፵ |
| ፵፮ | በእንተ ፡ ዘኢይደሉ ፡ አንሥኦ ፡ ሥእርተ ፡ ርእስ ፡ | ፻፵፪ |
| ፵፯ | በእንተ ፡ ስዒረ ፡ ሰንበት ፡ ወአክብሮ ፡ | ፻፵፬ |
| ፵፰ | በእንተ ፡ ሚጠት ፡ ኀበ ፡ ንስሐ ፡ | |
| ፵፱ | ከስአልናከ ፡ በፊት ፡ የሚጸለይ ፡ ከዳዊት ፡ መዝሙርና ፡ ከነቢያት ፡ መዝሙር ፡ | ፻፵፰ |
| ፶ | ሰአልናከ ፡ | ፻፶ |
| ፶፩ | ባሕረ ፡ ሐሳብ ፡ (ጉልቄ ፡ ዘመን) ፡ | ፻፷፯ |

# መርሐ ትልቈ ዘመን ዘኢትዮጵያ።

| ዓ፡ም፡ | ወንጌላዊ | የዘመን መለወጫ ቀን | አበቅቴ | መጥቅዕ | ጾመ ነነዌ | ዐቢይ ጾም | ደብረ ዘይት | ሆሣዕና | ስቅለት | ትንሣኤ | ርክበ ካህናት | ዕርገት | ጰራቅሊጦስ | ጾመ ሐዋርያት | ጾ ድኅ… |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ፲፱፻፱ | ማቴዎ | እሑድ | ፫ | ፳፯ | ጥር ፳፱ | የካ ፲፫ | መ ፲ | ሚያዝያ ፩ | ሚያዝ ፮ | ሚ ፰ | ግን ፪ | ግን ፲፯ | ግን ፳፯ | ግን ፳፰ | ግን |
| ፲፱፻፲ | ማርቆስ | ሰኞ | ፲፬ | ፲፮ | ጥር ፳፩ | የካ ፭ | መ ፪ | መጋ ፳፫ | መጋቢ ፳፰ | መጋ ፴ | ሚ ፳፬ | ግን ፱ | ግን ፲፱ | ግን ፳ | ግን |
| ፲፱፻፲፩ | ሉቃስ | ማክሰ | ፳፭ | ፭ | የካ ፲፩ | የካ ፳፭ | መ ፳፪ | ሚያዝ ፲፫ | ሚያዝ ፲፰ | ሚ ፳ | ግን ፲፬ | ግን ፳፱ | ሰኔ ፱ | ሰኔ ፲ | ሰኔ |
| ፲፱፻፲፪ | ዮሐንስ | ሐሙስ | ፮ | ፳፬ | የካ ፪ | የካ ፲፮ | መ ፲፫ | ሚያዝያ ፬ | ሚያዝያ ፱ | ሚ ፲፩ | ግን ፭ | ግን ፳ | ግን ፴ | ሰኔ ፩ | ሰኔ |
| ፲፱፻፲፫ | ማቴዎ | ዓርብ | ፲፯ | ፲፫ | የካ ፲፭ | የካ ፳፱ | መ ፳፮ | ሚያዝ ፲፯ | ሚያዝ ፳፪ | ሚ ፳፬ | ግን ፲፰ | ሰኔ ፫ | ሰኔ ፲፫ | ሰኔ ፲፬ | ሰኔ |
| ፲፱፻፲፬ | ማርቆስ | ቅዳሜ | ፳፰ | ፪ | የካ ፯ | የካ ፳፩ | መ ፲፰ | ሚያዝ ፱ | ሚያዝ ፲፬ | ሚ ፲፮ | ግን ፲ | ግን ፳፭ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፮ | ሰኔ |
| ፲፱፻፲፭ | ሉቃስ | እሑድ | ፱ | ፳፩ | ጥር ፳፱ | የካ ፲፫ | መ ፲ | ሚያዝ ፩ | ሚያዝያ ፮ | ሚያ ፰ | ግን ፪ | ግን ፲፯ | ግን ፳፯ | ግን ፳፰ | ግን |
| ፲፱፻፲፮ | ዮሐንስ | ማክሰ | ፳ | ፲ | የካ ፲፰ | መጋ ፪ | መ ፳፱ | ሚያዝ ፳ | ሚያዝ ፳፭ | ሚ ፳፯ | ግን ፳፩ | ሰኔ ፮ | ሰኔ ፲፮ | ሰኔ ፲፯ | ሰኔ |
| ፲፱፻፲፯ | ማቴዎ | ረቡዕ | ፩ | ፳፱ | የካ ፫ | የካ ፲፯ | መ ፲፬ | ሚያዝያ ፭ | ሚያዝ ፲ | ሚ ፲፪ | ግን ፮ | ግን ፳፩ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፪ | ሰኔ |
| ፲፱፻፲፰ | ማርቆስ | ሐሙስ | ፲፪ | ፲፰ | ጥር ፳፭ | የካ ፱ | መ ፮ | መጋቢ ፳፯ | ሚያዝያ ፪ | ሚያ ፬ | ሚ ፳፰ | ግን ፲፫ | ግን ፳፫ | ግን ፳፬ | ግን |
| ፲፱፻፲፱ | ሉቃስ | ዓርብ | ፳፫ | ፯ | የካ ፲፭ | የካ ፳፱ | መ ፳፮ | ሚያዝ ፲፯ | ሚያዝ ፳፪ | ሚ ፳፬ | ግን ፲፰ | ሰኔ ፫ | ሰኔ ፲፫ | ሰኔ ፲፬ | ሰኔ |
| ፲፱፻፳ | ዮሐንስ | እሑድ | ፬ | ፳፮ | ጥር ፳፱ | የካ ፲፫ | መ ፲ | ሚያዝያ ፩ | ሚያዝያ ፮ | ሚ ፰ | ግን ፪ | ግን ፲፯ | ግን ፳፯ | ግን ፳፰ | ግን |
| ፲፱፻፳፩ | ማቴዎ | ሰኞ | ፲፭ | ፲፭ | ጥር ፳፩ | የካ ፭ | መ ፪ | መጋ ፳፫ | መጋቢ ፳፰ | መ ፴ | ሚ ፳፬ | ግን ፱ | ግን ፲፱ | ግን ፳ | ግን |
| ፲፱፻፳፪ | ማርቆስ | ማክሰ | ፳፮ | ፬ | የካ ፲፩ | የካ ፳፭ | መ ፳፪ | ሚያዝ ፲፫ | ሚያዝ ፲፰ | ሚ ፳ | ግን ፲፬ | ግን ፳፱ | ሰኔ ፱ | ሰኔ ፲ | ሰኔ |
| ፲፱፻፳፫ | ሉቃስ | ረቡዕ | ፯ | ፳፫ | ጥር ፳፮ | የካ ፲ | መ ፯ | መጋቢ ፳፰ | ሚያዝያ ፫ | ሚ ፭ | ሚ ፳፱ | ግን ፲፬ | ግን ፳፬ | ግን ፳፭ | ግን |
| ፲፱፻፳፬ | ዮሐንስ | ዓርብ | ፲፰ | ፲፪ | የካ ፲፭ | የካ ፳፱ | መ ፳፮ | ሚያዝ ፲፯ | ሚያዝ ፳፪ | ሚ ፳፬ | ግን ፲፰ | ሰኔ ፫ | ሰኔ ፲፫ | ሰኔ ፲፬ | ሰኔ |
| ፲፱፻፳፭ | ማቴዎ | ቅዳሜ | አልቦ | ፴ | የካ ፯ | የካ ፳፩ | መ ፲፰ | ሚያዝ ፱ | ሚያዝ ፲፬ | ሚ ፲፮ | ግን ፲ | ግን ፳፭ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፮ | ሰኔ |
| ፲፱፻፳፮ | ማርቆስ | እሑድ | ፲፩ | ፲፱ | ጥር ፳፪ | የካ ፮ | መ ፫ | መጋቢ ፳፬ | መጋቢ ፳፱ | ሚ ፩ | ሚ ፳፭ | ግን ፲ | ግን ፳ | ግን ፳፩ | ግን |
| ፲፱፻፳፯ | ሉቃስ | ሰኞ | ፳፪ | ፰ | የካ ፲፪ | የካ ፳፮ | መ ፳፫ | ሚያዝ ፲፬ | ሚያዝ ፲፱ | ሚ ፳፩ | ግን ፲፭ | ግን ፴ | ሰኔ ፲ | ሰኔ ፲፩ | ሰኔ |
| ፲፱፻፳፰ | ዮሐንስ | ረቡዕ | ፫ | ፳፯ | የካ ፫ | የካ ፲፯ | መ ፲፬ | ሚያዝ ፭ | ሚያዝ ፲ | ሚ ፲፪ | ግን ፮ | ግን ፳፩ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፪ | ሰኔ |
| ፲፱፻፳፱ | ማቴዎ | ሐሙስ | ፲፬ | ፲፮ | ጥር ፲፰ | የካ ፪ | የካ ፳፱ | መጋቢ ፳ | መጋቢ ፳፭ | መ ፳፯ | ሚ ፳፩ | ግን ፮ | ግን ፲፮ | ግን ፲፯ | ግን |
| ፲፱፻፴ | ማርቆስ | ዓርብ | ፳፭ | ፭ | የካ ፰ | የካ ፳፪ | መ ፲፱ | ሚያዝ ፲ | ሚያ ፲፭ | ሚ ፲፯ | ግን ፲፩ | ግን ፳፮ | ሰኔ ፮ | ሰኔ ፯ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፩ | ሉቃስ | ቅዳሜ | ፮ | ፳፬ | ጥር ፴ | የካ ፲፬ | መ ፲፩ | ሚያዝያ ፪ | ሚያ ፯ | ሚ ፱ | ግን ፫ | ግን ፲፰ | ግን ፳፰ | ግን ፳፱ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፪ | ዮሐንስ | ሰኞ | ፲፯ | ፲፫ | የካ ፲፱ | መጋ ፫ | መ ፴ | ሚያዝ ፳፩ | ሚያዝ ፳፮ | ሚ ፳፰ | ግን ፳፪ | ሰኔ ፯ | ሰኔ ፲፯ | ሰኔ ፲፰ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፫ | ማቴዎ | ማክሰ | ፳፰ | ፪ | የካ ፬ | የካ ፲፰ | መ ፲፭ | ሚያዝያ ፮ | ሚያ ፲፩ | ሚ ፲፫ | ግን ፯ | ግን ፳፪ | ሰኔ ፪ | ሰኔ ፫ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፬ | ማርቆስ | ረቡዕ | ፱ | ፳፩ | ጥር ፳፮ | የካ ፲ | መ ፯ | መጋ ፳፰ | ሚያዝያ ፫ | ሚ ፭ | ሚ ፳፱ | ግን ፲፬ | ግን ፳፬ | ግን ፳፭ | ግን |
| ፲፱፻፴፭ | ሉቃስ | ሐሙስ | ፳ | ፲ | የካ ፲፮ | የካ ፴ | መ ፳፯ | ሚያዝ ፲፰ | ሚያዝ ፳፫ | ሚ ፳፭ | ግን ፲፱ | ሰኔ ፬ | ሰኔ ፲፬ | ሰኔ ፲፭ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፮ | ዮሐንስ | ቅዳሜ | ፩ | ፳፱ | የካ ፯ | የካ ፳፩ | መ ፲፰ | ሚያዝ ፱ | ሚያ ፲፬ | ሚ ፲፮ | ግን ፲ | ግን ፳፭ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፮ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፯ | ማቴዎ | እሑድ | ፲፪ | ፲፰ | ጥር ፳፪ | የካ ፮ | መ ፫ | መጋቢ ፳፬ | መጋቢ ፳፱ | ሚ ፩ | ሚ ፳፭ | ግን ፲ | ግን ፳ | ግን ፳፩ | ግን |
| ፲፱፻፴፰ | ማርቆስ | ሰኞ | ፳፫ | ፯ | የካ ፲፪ | የካ ፳፮ | መ ፳፫ | ሚያዝ ፲፬ | ሚያ ፲፱ | ሚ ፳፩ | ግን ፲፭ | ግን ፴ | ሰኔ ፲ | ሰኔ ፲፩ | ሰኔ |
| ፲፱፻፴፱ | ሉቃስ | ማክሰ | ፬ | ፳፮ | የካ ፬ | የካ ፲፰ | መ ፲፭ | ሚያዝ ፮ | ሚያዝ ፲፩ | ሚ ፲፫ | ግን ፯ | ግን ፳፪ | ሰኔ ፪ | ሰኔ ፫ | ሰኔ |
| ፲፱፻፵ | ዮሐንስ | ሐሙስ | ፲፭ | ፲፭ | ጥር ፲፰ | የካ ፪ | የካ ፳፱ | መጋቢ ፳ | መጋ ፳፭ | መ ፳፯ | ሚ ፳፩ | ግን ፮ | ግን ፲፮ | ግን ፲፯ | ግን |
| ፲፱፻፵፩ | ማቴዎ | ዓርብ | ፳፮ | ፬ | የካ ፰ | የካ ፳፪ | መ ፲፱ | ሚያዝ ፲ | ሚያ ፲፭ | ሚ ፲፯ | ግን ፲፩ | ግን ፳፮ | ሰኔ ፮ | ሰኔ ፯ | ሰኔ |

# መርሐ ትልቊ ዘመን ዘኢትዮጵያ።

| ዓ.ም. | ወንጌላዊ | የዘመን መለወጫ ቀን | አበቅቴ | መጥቅዕ | ጾመ ነነዌ | ዐቢይ ጾም | ደብረ ዘይት | ሆሣዕና | ስቅለት | ትንሣኤ | ርክበ ካህናት | ዕርገት | ጰራቅሊጦስ | ጾመ ሐዋርያት | ጾመ ድኅነት |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ፲፱፻፸፮ | ዮሐንስ | ሰኞ | ፳፰ | ፪ | የካ- ፭ | የካ ፲፱ | መ ፲፮ | ሚያዝያ ፯ | ሚያዝ ፲፪ | ሚ ፲፬ | ግን ፰ | ግን ፳፫ | ሰኔ ፫ | ሰኔ ፬ | ሰኔ ፮ |
| ፲፱፻፸፯ | ማቴዎስ | ማክሰ | ፱ | ፳፩ | ጥር-፳፯ | የካ ፲፩ | መ ፰ | መጋ ፳፱ | ሚያዝያ ፬ | ሚያ ፮ | ሚያ ፴ | ግን ፲፭ | ግን ፳፭ | ግን ፳፮ | ግን ፳፰ |
| ፲፱፻፸፰ | ማርቆስ | ረቡዕ | ፳ | ፲ | የካ- ፲፯ | መጋ ፩ | መ ፳፰ | ሚያዝ ፲፱ | ሚያዝ ፳፬ | ሚ ፳፮ | ግን ፳ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፲፭ | ሰኔ ፲፮ | ሰኔ ፲፰ |
| ፲፱፻፸፱ | ሉቃስ | ሐሙስ | ፩ | ፳፱ | የካ- ፪ | የካ ፲፮ | መ ፲፫ | ሚያዝያ ፬ | ሚያዝያ ፱ | ሚ ፲፩ | ግን ፭ | ግን ፳ | ግን ፴ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፫ |
| ፲፱፻፹ | ዮሐንስ | ቅዳሜ | ፲፪ | ፲፰ | ጥር-፳፫ | የካ ፯ | መ ፬ | መጋ ፳፭ | መጋቢ. ፴ | ሚ ፪ | ሚ ፳፮ | ግን ፲፩ | ግን ፳፩ | ግን ፳፪ | ግን ፳፬ |
| ፲፱፻፹፩ | ማቴዎስ | እሑድ | ፳፫ | ፯ | የካ- ፲፫ | የካ ፳፯ | መ ፳፬ | ሚያዝ ፲፭ | ሚያዝያ ፳ | ሚ ፳፪ | ግን ፲፮ | ሰኔ ፩ | ሰ ኔ ፲፩ | ሰኔ ፲፪ | ሰኔ ፲፬ |
| ፲፱፻፹፪ | ማርቆስ | ሰኞ | ፬ | ፳፮ | ጥር ፳፰ | የካ ፲፪ | መ ፱ | መጋቢት ፴ | ሚያዝያ ፭ | ሚያ ፯ | ግን ፩ | ግን ፲፮ | ግን ፳፮ | ግን ፳፯ | ግን ፳፱ |
| ፲፱፻፹፫ | ሉቃስ | ማክሰ | ፲፭ | ፲፭ | ጥር- ፳ | የካ ፬ | መ ፩ | መጋቢ. ፳፪ | መጋቢ. ፳፯ | መ ፳፱ | ሚ ፳፫ | ግንቦ ፰ | ግን ፲፰ | ግን ፲፱ | ግን ፳፩ |
| ፲፱፻፹፬ | ዮሐንስ | ሐሙስ | ፳፮ | ፬ | የካ- ፱ | የካ ፳፫ | መ ፳ | ሚያዝ ፲፩ | ሚያዝ ፲፮ | ሚ ፲፰ | ግን ፲፪ | ግን ፳፯ | ሰኔ ፯ | ሰኔ ፰ | ሰኔ ፲ |
| ፲፱፻፹፭ | ማቴዎስ | ዓርብ | ፯ | ፳፫ | የካ- ፩ | የካ ፲፭ | መ ፲፪ | ሚያዝያ ፫ | ሚያዝያ ፰ | ሚያ ፲ | ግን ፬ | ግን ፲፱ | ግን ፳፱ | ግን ፴ | ሰኔ ፪ |
| ፲፱፻፹፮ | ማርቆስ | ቅዳሜ | ፲፰ | ፲፪ | የካ- ፲፬ | የካ ፳፰ | መ ፳፭ | ሚያዝ ፲፮ | ሚያዝ ፳፩ | ሚ ፳፫ | ግን ፲፯ | ሰኔ ፪ | ሰኔ ፲፪ | ሰኔ ፲፫ | ሰኔ ፲፭ |
| ፲፱፻፹፯ | ሉቃስ | እሑድ | አልቦ | ፴ | የካ- ፮ | የካ ፳ | መ ፲፯ | ሚያዝያ ፰ | ሚያዝ ፲፫ | ሚ ፲፭ | ግን ፱ | ግን ፳፬ | ሰኔ ፬ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፯ |
| ፲፱፻፹፰ | ዮሐንስ | ማክሰ | ፲፩ | ፲፱ | ጥር ፳፯ | የካ ፲፩ | መ ፰ | መጋ ፳፱ | ሚያዝያ ፬ | ሚያ ፮ | ሚያ ፴ | ግን ፲፭ | ግን ፳፭ | ግን ፳፮ | ግን ፳፰ |
| ፲፱፻፹፱ | ማቴዎስ | ረቡዕ | ፳፪ | ፰ | የካ ፲ | የካ ፳፬ | መ ፳፩ | ሚያዝ ፲፪ | ሚያዝ ፲፯ | ሚ ፲፱ | ግን ፲፫ | ግን ፳፰ | ሰኔ ፰ | ሰኔ ፱ | ሰኔ ፲፩ |
| ፲፱፻፺ | ማርቆስ | ሐሙስ | ፫ | ፳፯ | የካ ፪ | የካ ፲፮ | መ ፲፫ | ሚያዝያ ፬ | ሚያዝያ ፱ | ሚ ፲፩ | ግን ፭ | ግን ፳ | ግን ፴ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፫ |
| ፲፱፻፺፩ | ሉቃስ | ዓርብ | ፲፬ | ፲፮ | ጥር ፳፬ | የካ ፰ | መ ፭ | መጋ ፳፮ | ሚያዝያ ፩ | ሚያ ፫ | ሚ ፳፯ | ግን ፲፪ | ግን ፳፪ | ግን ፳፫ | ግን ፳፭ |
| ፲፱፻፺፪ | ዮሐንስ | እሑድ | ፳፭ | ፭ | የካ ፲፫ | የካ ፳፯ | መ ፳፬ | ሚያዝ ፲፭ | ሚያዝያ ፳ | ሚ ፳፪ | ግን ፲፮ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፲፩ | ሰኔ ፲፪ | ሰኔ ፲፬ |
| ፲፱፻፺፫ | ማቴዎስ | ሰኞ | ፮ | ፳፬ | ጥር ፳፰ | የካ ፲፪ | መ ፱ | መጋቢ. ፴ | ሚያ ፭ | ሚያ ፯ | ግን ፩ | ግን ፲፮ | ግን ፳፮ | ግን ፳፯ | ግን ፳፱ |
| ፲፱፻፺፬ | ማርቆስ | ማክሰ | ፲፯ | ፲፫ | የካ ፲፰ | መጋ ፪ | መ ፳፱ | ሚያዝያ ፳ | ሚያ ፳፭ | ሚ ፳፯ | ግን ፳፩ | ሰኔ ፮ | ሰኔ ፲፮ | ሰኔ ፲፯ | ሰኔ ፲፱ |
| ፲፱፻፺፭ | ሉቃስ | ረቡዕ | ፳፰ | ፪ | የካ ፲ | የካ ፳፬ | መ ፳፩ | ሚያዝ ፲፪ | ሚያ ፲፯ | ሚ ፲፱ | ግን ፲፫ | ግን ፳፰ | ሰኔ ፰ | ሰኔ ፱ | ሰኔ ፲፩ |
| ፲፱፻፺፮ | ዮሐንስ | ዓርብ | ፱ | ፳፩ | ጥር ፳፬ | የካ ፰ | መ ፭ | መጋቢ. ፳፮ | ሚያዝያ ፩ | ሚያ ፫ | ሚ ፳፯ | ግን ፲፪ | ግን ፳፪ | ግን ፳፫ | ግን ፳፭ |
| ፲፱፻፺፯ | ማቴዎስ | ቅዳሜ | ፳ | ፲ | የካ ፲፬ | የካ ፳፰ | መ ፳፭ | ሚያዝ ፲፮ | ሚያ ፳፩ | ሚ ፳፫ | ግን ፲፯ | ሰኔ ፪ | ሰኔ ፲፪ | ሰኔ ፲፫ | ሰኔ ፲፭ |
| ፲፱፻፺፰ | ማርቆስ | እሑድ | ፩ | ፳፱ | የካ ፮ | የካ ፳ | መ ፲፯ | ሚያዝያ ፰ | ሚያ ፲፫ | ሚ ፲፭ | ግን ፱ | ግን ፳፬ | ሰኔ ፬ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፯ |
| ፲፱፻፺፱ | ሉቃስ | ሰኞ | ፲፪ | ፲፰ | ጥር ፳፩ | የካ ፭ | መ ፪ | መጋቢ. ፳፫ | መጋ ፳፰ | መጋ ፴ | ሚ ፳፬ | ግን ፱ | ግን ፲፱ | ግን ፳ | ግን ፳፪ |
| ፪ሺ. | ዮሐንስ | ረቡዕ | ፳፫ | ፯ | የካ ፲ | የካ ፳፬ | መ ፳፩ | ሚያዝ ፲፪ | ሚያ ፲፯ | ሚ ፲፱ | ግን ፲፫ | ግን ፳፰ | ሰኔ ፰ | ሰኔ ፱ | ሰኔ ፲፩ |
| ፪ሺ፩ | ማቴዎስ | ሐሙስ | ፬ | ፳፮ | የካ ፪ | የካ ፲፮ | መ ፲፫ | ሚያዝያ ፬ | ሚያዝያ ፱ | ሚያ ፲፩ | ግን ፭ | ግን ፳ | ግን ፴ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፫ |
| ፪ሺ፪ | ማርቆስ | ዓርብ | ፲፭ | ፲፭ | ጥር ፲፯ | የካ ፩ | የካ ፳፰ | መጋቢ. ፲፱ | መጋ ፳፬ | መ ፳፮ | ሚያ ፳ | ግን ፭ | ግን ፲፭ | ግን ፲፮ | ግን ፲፰ |
| ፪ሺ፫ | ሉቃስ | ቅዳሜ | ፳፮ | ፬ | የካ ፯ | የካ ፳፩ | መ ፲፰ | ሚያዝያ ፱ | ሚያ ፲፬ | ሚ ፲፮ | ግን ፲ | ግን ፳፭ | ሰኔ ፭ | ሰኔ ፮ | ሰኔ ፰ |
| ፪ሺ፬ | ዮሐንስ | ሰኞ | ፯ | ፳፫ | ጥር ፳፰ | የካ ፲፪ | መ ፱ | መጋቢ. ፴ | ሚያዝያ ፭ | ሚያ ፯ | ግን ፩ | ግን ፲፮ | ግን ፳፮ | ግን ፳፯ | ግን ፳፱ |
| ፪ሺ፭ | ማቴዎስ | ማክሰ | ፲፰ | ፲፪ | የካ ፲፰ | መጋ ፪ | መ ፳፱ | ሚያዝያ ፳ | ሚያ ፳፭ | ሚ ፳፯ | ግን ፳፩ | ሰኔ ፮ | ሰኔ ፲፮ | ሰኔ ፲፯ | ሰኔ ፲፱ |
| ፪ሺ፮ | ማርቆስ | ረቡዕ | አልቦ | ፴ | የካ ፫ | የካ ፲፯ | መ ፲፬ | ሚያዝያ ፭ | ሚያዝያ ፲ | ሚ ፲፪ | ግን ፮ | ግን ፳፩ | ሰኔ ፩ | ሰኔ ፪ | ሰኔ ፬ |
| ፪ሺ፯ | ሉቃስ | ሐሙስ | ፲፩ | ፲፱ | ጥር ፳፭ | የካ ፱ | መ ፮ | መጋቢ. ፳፯ | ሚያዝያ ፪ | ሚያ ፬ | ሚ ፳፰ | ግን ፲፫ | ግን ፳፫ | ግን ፳፬ | ግን ፳፮ |
| ፪ሺ፰ | ዮንሐስ | ቅዳሜ | ፳፪ | ፰ | የካ ፲፬ | የካ ፳፰ | መ ፳፭ | ሚያዝ ፲፮ | ሚያ ፳፩ | ሚ ፳፫ | ግን ፲፯ | ሰኔ ፪ | ሰኔ ፲፪ | ሰኔ ፲፫ | ሰኔ ፲፭ |